# ጸጥላው ወልደ ዮሐንስ



አጭር የሕይወት ታሪክ
(ግለ ታሪክ)

# ምስጋና

ይህንን ያባቴን ግለታሪክና አንዳንድ ፎቶግራፎችን ያካበትን መፅሐፍ ለማደራጀትና ለማዘጋጀት ዕድሉንና አቅሙን ከሰጠኝ ልዑል እግዚአብሔር ክብር ምስጋና ይግባው ።

እናቴና ከሎችም ቤተ ሰቦች በፕሮጀክቱ በመተባበር ስላረጉት የሃሳብና የሞራል ድጋፍ እጅግ አመሰግናለሁ።

በሕትመቱና በዲዛይን ሥራ ጌታ መኮንን፣ ተዋነይ ስቱድዮ ከልብ አመሰግናለሁ።

ፍሥሐ አጥላው ወልደ ዮሃንስ

ዲማ ማተሚያ ቤት
አዲስ አበባ
2012

# መግቢያ

አባቴ አቶ አጥላው ወልደዮሃንስ በአምሳ አምስት ዓመቱ ይሠራበት ከነበረው የእርሻ ሚኒስትር ጡረታ ሲወጣ ከልጅነቱ ጀምሮ ያጋጠሙትን የተለያዩ ሁኔታዎች በጽሑፍ እንዲያሰፍርልኝ በጠየቁት መሠረት ጥንቅቅ እና ቅልጥፍ ባለ መልክ በእጁ ጽፎ፤ በታይፕም አስመትቶ ወደምኖርብት አሜሪካ አገር ልኮልኝ እስከዛሬ ድረስ (ከ30 ዓመት በላይ) ይዤው ቆይቻለሁ።

ይህንን የአባቴን የሚያስገርም ታሪክ ከጊዜ ጊዜ እያወጣሁ በግሌ ባነበውም አሁን ግን ለቤተሰብ እና ለወዳጆች ማካፈል ጠቃሚ መስሎ ስለታየኝ በ2012 በኢትዮጵያ አቆጣጠር እናቴን፤ ወይዘሮ ሐመረ ገብረ ፃድቅን ለማየት ኢትዮጵያ ስመጣ ልዩ ልዩ ፎቶ ግራፎችን ጨምሬ አባቴ ራሱን እንደጻፈው ለማሳተም ወሰንኩ።

ምንም የአባቴ ታሪክ የእግዚአብሔርን ድንቅ በረከትና ረድዔት የሚያሳይ ግሉ ታሪክ ቢሆንም፤ ከዚያም ላቅ ያለ ቁም ነገር እንዳለበት ተረድቻለሁ። በተለይ አባቴ በልጅነቱ የቤተ ክርስቲያን አገልግሎት ትምህርት፤ እናትና አባቱን ተለይቶ ደብረ ሊባኖስ ገዳም በነበረበት ጊዜ የፋሽስት አዛዥ የነበረው ግራዚያኒ በደብረ ሊባኖስ ቀሳውስትና ወጣት ተማሪዎች ላይ ያደረገውን ግፍና ጭፍጨፋ ለመጀመሪያ ጊዜ በዓይን ምስክርነት ፅፎ ለትውልድ ማስቀመጡ ታሪክን መዘከር ለሚወዱ ኢትዮጵያውያን ሁሉ ውለተኛ ነው እላለሁ።

"የደብረሊባኖስ ጭፍጭፋ" "THE DEBRE LIBANOS MASSACRE" ተብሎ የሚታወቀው ድርጊት ከአፈ - ታሪክ ተነስተው በቅርብ ጊዜ የዘገቡ የውጭ ፀሐፊዎች ቢኖሩም፤ በቦታው የነበረ፣ ከዕልቂቱ በተዓምራት ተርፎ የዓይን ምስክርነቱን መፃፉ ጠቃሚ የታሪክ ዘገባ እንደሆነ አስቀድሜ ያሳየኋቸው የታሪክ ተማራማሪ የሆኑ ወዳጆቼ አስተውለዋል። በዚህም ምክንያት ፅሁፉ እንዲታተም ሲገፋፉኝ ነበር። አሁን እግዚአብሔር የፈቀደው ጊዜ ደርሶ አሁን ለሕትመት በቅቷል።

ስለ አባቴ ሳስብ ብዙ ወደ አዕምሮዬ የሚመጡ ትውስቶችና መልካም ትዝታዎች ቢኖሩም በዋንነት የማስታውሳቸው እኔነቴንም የቀረፁኝ ሦስት አንኳር ነገሮች አሉ። እነሱም ፦

1. አባቴ በእግዚአብሔር ላይ የነበረው ፍፁምና ጠንካራ እምነትና የነበረው ፈሪሃ እግዚአብሔር
2. ዘመድ ባዕድ ሳይል ለሰዎች የነበረው ፍቅርና ቅን አስተሳሰብ በተቻለውም ሁሉ ለመርዳት የማይቆጠብ መሆኑ
3. ለኔ በግሌ የነበረው ፍቅር፣ ድጋፍና ማበረታታት ናቸው።

## መንፈሳዊ ሕይወትና ፈሪሃ እግዚአብሔር

አባባ ከልጅነቱ ጀምሮ ከመንፈሳዊነት ያልተለየ የእዚአብሔርን ማንነት በቅጡ የተረዳ ጠንካራ ክርስቲያን ነበር። በአደገባትና ዕድሜውን ሁሉ በኖረባት የኦርቶዶክስ ተዋህዶ ሃይማኖት ፍፁም የፀና የማያወላውል እምነት ነበረው።

በተግባርም ቤተክርስቲያናትንና ቀሳውስትን በመደገፍ፣ በተለይም ደግሞ በአደገበት በተጉለትና ቡልጋ አውራጃ አካባቢ፣ ያሉትን የወይን አምባ ቅድስት ማርያም ቤተ ክርስቲያንና የእቲሳ አቡነ ተክለ ሃይማኖት ቤተ ክርስቲያን ዘመኑን ሁሉ ሲረዳ የኖረ ነበር።

ለምሳሌ አሜሪካን አገር እያለሁ ሳያቋርጥ በየጊዜው ከሚፅፍልኝ ደብዳቤዎች መካከል አልፎ አልፎ እንዲህ የሚሉ ይገኙበት ነበር፡-

“… ፍሥሐ፤ የእመቤታችን የወይን አምባ ማርያም አጥሯ እኮ እየፈረሰ ነው፣ ጣራውም ማፍሰስ ጀምሯል… እንግዲህ የምትችለውን አድርግ…“ ይህን የመሳሰለ ማሳሰቢያ ከሰላምታ ደብዳቤዎቹ ውስጥ በመላክ በግሌም ሆነ ሌሎች ቤተሰብና ወዳጆችን በማሰባሰብ በጥገናና በዕድሳት እንድንሳተፍ ያደርግ ነበር።

ምንም እንኳን አባባ በኦርቶዶክስ ሃይማኖቱ ጠንካራ ቢሆንም በግሉ የሚያምነውን እግዚአብሔርን ስለሚያውቀው፣ የእዚአብሔርን ሥም የሚጠሩ የሌላ ቤተ ክርስቲያን አባላት (ካቶሊክ ወይንም ፕሮቴስታንት) አክብሮት ነበረው።

አሜሪካን አገር ለጉብኝት በሚመጣበት ጊዜ የነበርኩበት አካባቢ የኢትዮጵያውያን ቤተ ክርስቲያናት በቅርብ ስላልነበሩ እኔና ቤተሰቤ ከምንሳተፍባቸው የፈረንጆች የፕሮቴስታንት ቤተክርስቲያን አብረን በመሄድ ፀሎትና ምልጃውን ለሚያውቀው አንድ አምላክ ያደርስ ነበር።

## ለሰው የነበረው ፍቅርና ቅን አስተሳሰብ

አባባ ለእግዚአብሔር ያለው ፍቅርና እምነት ዕለት ዕለት በክርስቲያናዊ ምግባር ይታይ ነበር። ችግረኞችን ለመርዳት፣ የተጎሳቆሉትን ለማንሳት ፍፁም ቸል የማይል፣ አንዳንድ ጊዜም ከራሱም ቤተሰብ አስበልጦ እስኪመስለን ድረስ ዘመድ ባዕድ ሳይል ለሌሎች ደራሽ ነበር። ይህንንም ድርጊቱን ከሕፃንነት ዕድሜዬ ጀምሬ ሳስተውለውና ስገነዘበው የነበረ ነው።

ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ስለ ሕይወት ሲጠየቅ፣ የአንድ ሰው ሕይወት ትርጉም በሁለት ነገሮች ላይ ብቻ እንደሚጠቃለል በማቴዎስ ወንጌል 22፥37 ላይ ሲናገር፡-

"ጌታ አምላክህን በፍፁም ልብህ፣ በፍፁም ነፍስህ፣ በፍፁም ሃሳብህ ውደድ፣ ባልንጀራህን (ሌሎች ሰዎችን) እንደራስህ ውደድ"። አባባም ይህንን የጌታን ቃል በሕይወቱ ኖሮ፣ በ1995 ዓ/ም አምላኩን ወዶ ሰውን ረድቶ ወደሚወደው ጌታው ተሰበሰበ።

## አባትነት

ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ደቀ መዛሙርቱ እንዴት እንፀልይ አስተምረን ብለው ሲጠይቁት "በሰማያት የምትኖር አባታችን ሆይ" ብላችሁ ጀምሩ ብሏቸው ነበር። እኔም የሰማዩን አባቴን ፍቅር፣ ደግነትና ርህራሄ ለማወቅና ለመረዳት ተምሳሌት የሚሆን ምድራዊ አባት ስለተሰጠኝ ምንኛ ዕድለኛ እንደሆንኩ አልስተውም።

አባባ ከሕፃንነቴ ጅምሮ ልዩ የሆነ አባታዊ ፍቅር እያሳየኝ፣ በየደረስኩበት ሁሉ "ጎሽ የኔ ልጅ፣ በርታ" በማለት በትምህርቴም ሆነ ከትምህርት ውጭ በማደርጋቸው እንቅስቃሴዎች በሰፊው ሲያበረታታኝ የኖረ አባት ነው።

በ12ና በ14 ዓመት ዕድሜዬ የፃፍኳችውን ከሕፃን አዕምሮ የወጡ ድርሰቶችና መፅሐፍትን በወቅቱ የነበረውን ውጣ ውረድ ተቋቁሞ ማስታወቂያ ሚኒስቴር ድረስ አድርሶ እንዲታተም ሳንሱር አስደርጎ "ይታተም" የሚል የመንግስት ማኅተም ያለባቸው መፃህፍቶች በእጀ አሉ።

በ14 ዓመት ዕድሜዬ በአዲስ አበባ ዙርያና በመጨረሻም በአገር ፍቅር

ቴያትር ያሳየሁትን ድራማ (ደራሲ፣ ፕሮዲውሰርና ዳይሬክተር በመሆን) ከውጭ ሕዝብ ጋር አዳራሹ መጥቶ ለመጀመሪያ ጊዜ ሲያይና በጋዜጦች ላይም ፎቶግራፌን ሲያይ የተሰማው ደስታ ይህ ነው አይባልም። ለዚህም የቴያትሩን ተዋናዮች (ሁሉ የ7ኛ ክፍል ጓደኞቼ) እንድጋብዝበት 50 ብር ሸልሞኛል። (ከሽልማቱም ጋር የፃፈልኝ ወረቀት ፎቶ የኋላ ገፆች ላይ አሉ)።

በትምህርቴ፣ በሥራዬና በኑሮዬ ላገኘኋቸው ስኬቶችም የአባቴ መልካምን ቅን ሃሳብ፣ ምርቃትና ድጋፍ ሁልግዜም ተለይቶኝ አያውቅም። በሕይወትም ስላሳልፍኳቸው አንዳንድ ውጣ ውረዶች "አይዞህ ልጄ ይህም ያልፋል፣ የምታመነው አምላክህ ይረዳሃል" እያለ የሚያፅናናኝ ቀሪ ዘመኔን ሁሉ የሚከተለኝና የሚደግፈኝ እንደሆነ አልጠራጠርም።

ከዚህም በተረፈ ከልጅነቴ ጀምሮ ልዩ ልዩ ቦታ፣ በተለይም የተወለደበትን የተጉለትና ቡልጋ፣ የኮረማሽን አካባቢ ያሳየኝ ነበር። ከባላገር ዘመዶቹም በሣር ጎጇቸው በመደብ ላይ እየተኛሁ፣ ሥረ መሠረቴ ማን እንደሆነ እንዳልረሳው ያደረገው ሁሉ ትልቅ ውለታ ነው።

በዕለተ ሰንበትና ባገኘው ጊዜ ሁሉ ወደ ቤተ ክርስትያን ይዞን በመሄድ ለእግዚአብሔር ቤት ያለን አክብሮትና ፍቅር ጠንካራ እንዲሆን የማይፋቅ አሻራ ጥሎብን አልፏል።

በ1970ዎች መጨረሻ አካባቢም የኢትዮጵያን ፊደላትንና የአማርኛን ቋንቋ በኮምፒዩተር ለማስገባት በማደርገው ጥረት፣ ምንም የዘመናዊ ትምህርት ባይኖረውም፣ በሃሳብም ሆነ በማበረታታት አብሮኝ የነበርና ለሚያውቃቸው ሁሉ በኩራት ከማስተዋወቅ አይቆጠብም ነበር። በዚያን ጊዜ በቪኦኤና (VOA)በኢትዮጵያ ሬድዮ ያደርኩኋቸውን ቃለመጠይቆች ጊዜውን ጠብቆ ከመስማት አልፎ በካሴት ቀድቶ ለሰዎች ያሰማ ነበር ።



# አጥላው ወልደ ዮሐንስ

## አጭር የሕይወት ታሪክ

# መቅድም

አዲስ አበባ የካቲት 20 ቀን 1967 ዓ.ም.

ለውድ ልጄ ፍሥሐ አጥላው እንደምን ሰንብተሃል ጤናህስ እንዴት ነው? እኛ ሁላችንም ላንተ ከማሰብና ከመናፈቅ በስተቀር በጣም ደህና ነን ቸር አምላክ ይመስገን፤ ባለፈው ጊዜ የጻፍክልኝ ደብዳቤ በህዳር ወር መጀመሪያ ገደማ ደርሶኝ እስካሁን መልሱን ያልጻፍኩልህ፣ የጠየቅኸኝን እስኪዘጋጅ በማለት ነበር፤ በደብዳቤህ እንደገለጽከው የጊዜ እጥረት ስላለብኝ በዕረፍት ጊዜ እያዘጋጀሁ ጨርሼ ይኸው አሁን ተጠናቆልኛል።

የነገሩም መነሻ የኔን የሕይወት ታሪክ በመዘርዘር፤ በኢትዮጵያ የብሔራዊ ትምህርት ሁኔታ (ቀደም ባለው ዘመን) የነበረውን በመጠኑ የሚያስረዳ ነው፤ የጀመርኩትን አዘጋጅቼ ልጨርስ እጽፍለታለሁ በማለት፣ አስቤ ስለበረ ምንም ጽሑፉ ተከታትሎ ቢደርስህ ይኸንኑ ለመግለጽ ዛሬ ልጽፍልህ ቻልኩ፤ ከሁሉም ደስ ያለኝ በራሴ ላይ የደረሰውን ማናቸውንም የኑሮ አቋም የትምህርት ሁኔታ በዓይኑ ያየሁትን በጆሮዬ የሰማሁትን ከአባቶቻችንም የሰማሁትን እውነተኛ ነገር አዘጋጅቼ ባንተ በኩል ላሰብከው የሪሰርች ማሟያ ሊረዳህ በመቻሉ ነው፤ ይህም አንድ ሰው ለምሳሌ ለእኔ ከአምሳ ዘመናት በላይ ባለ ጊዜ ያጋጠመውን ታሪክ ነክ የዕድሜ ጉዞ ለማስረዳትና ወደፊት ልልጆቹ የታሪክ ማስታወሻ ለማቆየት የሚችልበት ምክንያት ሲያጋጥመውና እጅግ ከፍ ያለ የመንፈስ ደስታ እንደሚሰጠው ይሰማኛል። ለሁሉም ጽሑፉን በካሴት ካስቀረጽኩት በኋላ በሁለት ሳምንት ውስጥ እንዲደርስህ አደርጋለሁ፤ ካሴቱን ግን እዚህ አገር የመጣው ጓደኛህ ሲመለስ ለሱ እልክልሃለሁ፤ በተጨማሪም የአማርኛ መዝገበ ቃላት (ዲክሺኔሪ) በደንብ ሆኖ ስለታተመ እሱንም ልልክልህ አስቤአለሁ ምናልባት። ይጠቅምህ ይሆናል ትንሽ ክብደት ያለው መጽሐፍ ነው።

# አጥላው ወልደ ዮሐንስ አጭር ሕይወት ታሪክ

1ኛ/ ከ1912 እስከ 1927 ዓ.ም በወላጆች ቤት 15 ዓመት

2ኛ/ ከ1927 እስከ 1929 ዓ.ም በትምህርት ቤት 2 ዓመት

3ኛ/ ከ1929 እስከ 1933 ዓ.ም በጠላት ዘመን 4 ዓመት

4ኛ/ ከ1933 እስከ 1967 ዓ.ም በመንግሥት ሥራ 34 ዓመት

ቸርነቱ የማይወሰን ልዑል እግዚአብሔር እያንዳንዳችንን ሲፈጥር የተወሰነልንን ዕድሜ በምን ዓይነት ኑሮ እንደምንፈጽም፣ እሱ ባወቀ በሰጠን እድል የዚህን ዓለም የመከራና የደስታ ጉዞ ያየን፣ በማየት ላይ ያለን፣ ወደፊትም ለማየት ተሰልፈን እንገኛለን።

እኔም የዚሁ ሰልፍ ተካፋይ የሆንኩት አጥላው ወልደ ዮሐንስ ከተወለድኩበት ከ1912 ዓ.ም ጀምሮ እስከ 1967 ዓ.ም ድረስ በዚህ በ55 ዘመን ውስጥ የነበርኩበትን የኑሮ አቋም የሚያስረዳ/ሕይወት ታሪክ/ከዚህ ቀጥዬ ባጭሩ ጽፌአለሁ።

ይህም እግዚብሔር በኔ በአነስተኛው ፍጡሩ ላይ ያደረገውን ተዓምራዊ ሥራ ለመግለጽ ብዬ ነው እንጂ፣ ከታሪክ የሚያበቃ ሥጋዊም ሆነ መንፈሳዊ ሥራ የፈጸምኩት ኑሮ አይደለም።

<u>የሕይወት ታሪኩም ቀጥሎ ያለው ነው</u>

በሸዋ ጠቅላይ ግዛት በተጉለትና ቡልጋ አውራጃ በከሰም ወረዳ ቡልጋ ወይን አምባ ቀበሌ በ1912 ዓ.ም ሰኔ 30 ቀን እሁድ በዘመነ ዮሐንስተወለድኩ። የተወለድኩትም በእናት አባቴ ቤት ሲሆን በሕፃንነት ወራት የነበረኝ አስተዳደግ እንደት እንደሆነ ራሴ ባላውቀውም ዕድሜዬ ከፍ ሲል ወላጆቼ ሲያወሩ እንደሰማሁት በሕፃን ልጅ ጠባይ የማልቀስና የመቅበጥበጥ ሁኔታ የለበትም ይሉ ነበር። ዕድሜዬ 5 ዓመት በሚደርስበት ጊዜ አጎቴ ደብተራ ምንደሲል የተባሉ የኮረማሽ ሚካኤል ቤተክርስቲያን ኃላፊ ሆነው፣ ባገሩም

የታወቁና የተከበሩ ሰው ስለነበሩ፣ አሳቸው ዘንድ እንድቀመጥ ተደረገ። አሳቸውም መሸሻ የተባለ አንድ ልጅ ብቻ ስለነበራቸውና በእድሜም እኩል ስለነበርን ከሱ ጋር እንዳድግ አደረጉ። ቤተክርስቲያኑም ቅርብ ስለነበር አልፎ አልፎ ከመሸሻ ጋር እየሄድን ፊደል መቁጠር ጀመርን፣ እናቴም ከወይን ቶሎ ቶሎ እየመጣች ታየኝ ነበር።

እኔም ዕድሜዬ ለባላገር ኑሮ ለከብት እረኝነት፣ ለመካካከ በቂ ሆኖ ስለነበረ አባቴንና የእንጀራ እናቴን በቅንነት እያገለገልኩ እጅግ ያመሰግኑኝ፣ ይመርቁኝም ነበር። በዚሁ ጊዜም ቢሆን እናቴ አልፎ አልፎ እየመጣች እኔን ከማየት አላቋረጠችም። እስከ 12 ዓመት እድሜዬ ድረስ በዚሁ ተግባር ያደረግሁት መልካም አገልግሎትና የተቀበልኩትም ምርቃት ምንጊዜም ሊዘነጋኝ አይችልም።

ከዚህ በኋላ እስከ 15 ዓመት ባለው ዕድሜዬ ማናቸውንም የግብርና ሙያ ያከረዳት አሠራለሁ፣ ባንዳንድ በዓልና እረፍት ጊዜ ወደ ቤተክርስቲያን እየሄድኩ ቀደም ብዬ አጐቴ ቤት ጀምሬ የነበረውን ትምህርት እቀጥል ነበር።

ኃይሉ የተባለ የደብተራ አብተየስ ልጅ ከትምህርት ቤት ስሄድ አስተማሪዬ ደብተራ ሀበነ እያዘዙት ያስተምረኝ ስለነበረ በየጊዜው ስለትምህርት ጠቃሚነት ያወራኛል። እኛ ቤትም አብረን እየሄድን የኔን የትምህርት ጉብዝና ለአባቴ ይነግራቸው ስለነበረ ደስ ይላቸዋል። ነገር ግን ሥራዬን ትቼ ሙሉ ጊዜዬን ትምህርት ቤት ለማድረግ ቤተሰቦቼም ቢፈቅዱልኝ ከሌላው ሥራዬ በጣም አስብ ስለነበረ አልፎ አልፎ ካልሆነ በስተቀር ሥራ ባለ ቀን ወደ ትምህርት ቤት ለመሄድ ብጓጓም የሥራው ሁኔታ የበለጠ ያሳስበኝ ነበር።

በዚህ ዓይነት ጥቂት ጊዜ እንደቆየሁ ኢካይ ሥሙን የጠቀስኩት ኃይሉ አብተየስ ድንገት ሳላስበው "ለትምህርት ወደ አሩቅ አገር መሄደ ስለሆነ ከኔ ጋር እንሂድ" አለኝ። እኔም ያላሰብኩት እንግዳ ነገር ቢሆንብኝም እሺ አልኩት። እንግዲያውስ እስከ ሦስት ቀን ድረስ ተዘጋጅ ብሎ አስጠነቀቀኝ። እኔም ምንም ሳላመነታና ችግር ይገጥመኛል ብዬ ሳልሰጋ ለስንቅ የሚሆን አንዳች ነገር ሳይኖረኝ በበዓል ቀን የምለብሰውን ኩታ ሱሪ እና ጠባብና ኮት በአንድ ከረጢት ውስጥ አድርጌ የዘወትር ልብሴን እንደለበስኩ አንድ ጋቢ በተጨማሪ ይዤ ተዘጋጀሁ።

ኃይሉንም እንደነገ ልንሄድ አግኝቼው ልብስህን ያዝና በጧት ከቤትህ ወጥተህ ቆየኝ ስላለኝ በተባለው ሰዓት ጠብቆው መጋቢት 4 ቀን 1926 ዓ.ም ተነስተን እቲሳ ተክለ ሃይማኖት አድረን በማግስቱ ጉዞአችንን በመቀጠል አሩፋ ከሚባል አገር ስንደርስ የመጋቢት አቦ ዋዜማ ስለነበረ አቤቱ ክርስቲያን በዋዜማው በዓል ላይ ተካፋይ በመሆን ከካህናቱ ጋር ግብዣ ተደርጐልን አደርን። በማዕግስቱም ታቦቱ እስኪነግሥ ድረስ ቆይተን ስለነበረ እንድናድር ስለጋበዙን እዚያው አዳር ሆነና በማዕግስቱ በጧት ተነስተን ጉዟችንን ቀጠልን።

መንገዳችንም ጊዳና ወበሪ በተባለው አገር ስለነበረ በመንገድ ላይ በምንጓዝበት ጊዜ ቤተክርስቲያን ያለበትን ስፍራ ተጠግተን ስለምናደርግ ብዙ ችግር አላጋጠመንም። ኃይሉም ለመንገድ ስንቅ የሚሆን ዳቦ ቆሎና በሶ እንዲሁም ቆሎ በሸልቻ ይዞ ስለነበረ ከተያዘው ስንቅ ምንም ያህል ሳንነካለት በሦስተኛው ቀን ደብረ ሊባኖስ ገባን። በመንገድ ላይ አልፎ አልፎ ሲርበንና ውኃ ሲጠማን ትልልቅ መንደር እየተመለከትን ሁለታችንም ወደበሩ ጠጋ ብለን በመቆም "ምንተ ስሟ ለማርያም" በማለት ድምጽ ስናሰማ የመንደሩ ውሾች ሁሉ ተሰብስበው ይጮሁብናል። ባለቤቶችም ተማሪዎች ከውጭ ቆመዋልና ተዘከሯቸው ይላሉ። አንዳንዶቹም ከቤት አስገብተው ምሳችንን አብልተው ጠላም ሰጥተውን ውሾች እንዳይነክሱን ከውጭ ድረስ ወጥተው ይሸኙን ነበር።

ደብረ ሊባኖስ እንደደረስን ከገዳሙ አቅራቢያ የኃይሉ ታላቅ እህት የወይዘሮ ጽጌ አብተየስ ቤት ስለነበረ ሳይታሰብ ድንገት በመምጣታችንና ወንድሟን በማግኘቷ በጣም ደስ አላት። ምንም እኔን አስቀድሞ ባታውቀኝም አባቴንና እናቴን በደንብ ስለምታውቃቸው "አይ ኃይሉ - ጉደኛ ነህ - እንዴት ይዘኸው መጣህ? እግዚብሔር ይይልህ፣ ያባቱ ቤት እንኳን ለሱ ለማንም የተረፈ ነው፣ እኔ አውቀዋለሁ፣ አንተስ ልጅ እንዴት ጨከንክና ከቤትህ ተለየህ፣ አይ ያች ደጓ እናትህ ወለተየስ ይህን ጊዜ ምን ትሆነው ይሆን" መቸስ ምን ይደረግ የተክልዬ ፈቃዳቸው ቢሆን ነው፣ የናትና ያባትህ አምላክ ይጠብቅህ፣ በሉ አሁንም እዚሁ ሁለት ሦስት ቀን ቆዩና ትምህርት ቤት ተጠይቆ ደህና ቦታ ይገባል ተባለና እዚያው አደርን።

የወይዘሮ ጽጌ ባለቤትም አቶ አስፋው አባ ተስፋ ጊዮርጊስ ዘንድ ተማሪ ይበዛል፣ በሽታም አይታጣ፣ ከቤተ ክርስቲያኑ አጠገብ ካለው አባ ገብረ

ሚካኤል ትምህርት ቤት እንዲገባ እንጠይቅለታለን አሉ። የገባነው ቅዳሜ ቀን ስለነበረ በማዕግሥቱ እሁድ እነሱም ቤተክርስቲያን የሚሳለሙት እዚያው አቡነ ተክለሃይማኖት ገዳም ስለሆነ ሁላችንም አብረን ሔድንና አስቀድስን እኔና ኃይሉ ጠበል ስንጠመቅ ድረስ አቶ አስፋውና ወይዘሮ ጽጌ አባ ገብረ ሚካኤል ዘንድ ሔደው ጠይቀዋቸው ለጊዜው ጥቂት አሟቸው ኖሮ በተሻለች ሰዓት ታመጡታላችሁ ብለው የመለሷቸው መሆኑን ገለጹልን።

ኃይሉም ለመግባት የሚፈልገው ቀድሞ ከነበረበት ከዜማ ትምህርት ቤት ስለሆነ እዚያው ድረስ ከኔ ጋር ሄዶ የዜማውን አስተመሐሪ ካነገጋገሯቸው በኋላ እንዲማር ፈቅደውለት ለማረፊያ የሚሆን ቤትም ሰጡት፣ ዱሮ የሚያቃቸውን ተማሪዎችም ስላገኘ ደስ አለው እኔንም አስተዋወቀኝ።

በዚሁ ቀን እኔ ወይዘሮ ጽጌ ቤት ተመልሰን አደርንና በማዕግስቱ ሰኞ ጧት ዕቃችንን ይዘን ኃይሉ ወደሚማርበት የዜማ ትምህርት ቤት ሄድንና ቀደም ብሎ ከሰጡን ክፍል አረፍን። እሱም ወዲያውኑ ትምህርቱን ጀመረ። እዚያ የሚገኘው ተማሪ ሁሉ በሙሉ የሚማረው ዜማ ስለሆነ እኔ ቀንም ሆነ ማታ የነሱን ድምፅ በማዳመጥ ጊዜውን አሳልፍ ነበር። ሆኖም ኃይሉ በእረፍቱ ጊዜ አልፎ አልፎ ከክፍላችን ውስጥ የመጽሐፍ ንባብ ያስተምረኝ ነበር። በዚሁ ዓይነት አንድ ሳምንት ያህል ቆይቼ አባ ገብረ ሚካኤል ልጁን አምጡት ብለዋል ስለተባለ አቶ አስፋውና ወይዘሮ ጽጌ መጥተው ወሰዱኝ። አባ ገብረ ሚካኤልም አንድ 30 የሚሆኑ ተማሪዎቻቸው መካከል ቁጭ ብለው ሲያስተምሩ አገኘናቸው። እሳቸውም እንኳን መጣችሁ አሉና - "ይኸማ መልካም ልጅ ነው፥ ካሁን በፊት ጀምረሃል?" ብለው ጠየቁኝ እኔም በመጠኑ ነው እንጂ ብዙ አልተማርኩም አልኳቸው። "እንግዲህ ከዛሬ ጀምሮ የኔ ልጅ ነህ ትምህርትህን በደንብ ጠንክረህ መማር ነው፣ ብለው እነሱንም ምሳቸውን ጋበዟቸውና አሰናበቷቸው።

ወራቱ የሁዳዴ ጾም በመሆኑ ማናቸውም ትልቅም ሆነ ትንሽ ተማሪ እህል የሚቀምሰው የቤተክርስቲያን ደወል እየሰማ ከቅዳሴ ውጭ ስለሆነ ይኸንኑ እስክለምደው ድረስ ለጥቂት ቀን ተቸግሬ ነበር። ገዳሙም በጾም ቀን ቅዳሴ የሚወጡትም በ9 ሰዓት እንጂ እንደሌላው ስፍራ አይደለም።

አስተመሐሪዬም አባ ገብረ ሚካኤል ራሳቸው የሚያስተምሯቸውና

የሚከታተሏቸው ከፍተኛ ክፍል ያሉትን እንጂ እንደኔ ዝቅተኛ ክፍል ያሉትን የሚያስተምሯቸው ተማሪዎች በየተራ እየታዘዙ ነው፣ አለቃም አላቸው፣ እኔን ግን የንባብም ሆነ የማታ ቃል ትምህርት አጠገባቸው ሆኜ እንድማር ስላደረጉ ማናቸውንም በቅርብ ይከታተሉኝ ነበር።

ከተማሪዎቹ ውስጥ ሥዩም ገብረ እግዚአብሔር የተባለ የዚያው አገር ተወላጅ ስለነበረ ከሱ ጋር አንድ ክፍል እንድንቀመጥ አደረጉን። ሥዩምን በዕድሜ እኔ የምበልጠው ሲሆን እሱ ግን በትምህርት ይበልጠኝ ነበር።

እዚያ በገባሁ በሦስተኛው ሳምንት ከአስተመሐሪያችን ከገዳሙ የሚሰጣቸውን ድርጐ፣ ዳቤ፣ ንፍሮ እሁድ እሁድ ሲሆን ወጥ፣ ጠላ ጭምር እየተቀበለ የሚያመጣው ልጅ ትምህርት ቤቱን ለቆ ስለሄደ እኔ እየተቀበልኩ እንድረከብ አደረጉኝ።

በሳምንት እሁድ እሁድ ወይዘሮ ጽጌ እንጀራ በወጥ ወይም ዳቦ ባገልግል እያደረገች ታመጣልናለች። ለአስተመሐሪያችንም የሚስማማቸው እሷ ያመጣችው ምግብ ነበር። ከገዳም የሚመጣውን እህልና ውሃ የምንጠቀምበት እኔና ሥዩም ነበርን እንጂ አስተመሐሪያችን ጤና ስለሌላቸው ብዙ አይመገቡም። ሥዩም አገሩ እዚያው አካባቢ በመሆኑና አባትና እናቱም አጋፋሪ ገብረ እግዚአብሔር ወይዘሮ አሰገደች የታወቁ ባለርስት ሃብታሞች ስለሆኑ ከነሱ ቤት የሚመጣ በየዓይነቱ የሆነ ብዙ ምግብ ነበር።

ለአስተመሐሪያችንም ከገዳም የሚመጣው ድርጎ በየዕለቱ ስለሆነ ያደረውን ምግብ ስንቅ ለሌላቸው ተማሪዎች እንሰጣቸዋለን። በዚህ ዓይነት ትምህርቴን ስቀጥል ደብረ ሊባኖስ በመጣሁ በሦስተኛው ወር ገደማ ድንገት ሳይታሰብ በትምህርት ፕሮግራም ላይ እንዳለን አባቴና ሌሎችም ሰዎች እኔን ፍለጋ ድንገት ከተፍ አሉ። እኔም ለጊዜው ደነገጥኩና የናፍቆት ለቅሶ እያንቀጠቀጠኝ ሳለቅስ፣ አባቴ “ነፍስህ አለ ልጄ” ብሎ ሳመኝና እንደኔው ያለቅስ ጀመር። አስተምሐሪዬም አባቴ መሆኑን ሳይጠይቁ እንዲሁ አውቀው የአባባ መምጣት ምንም ያልጠበቁት ስለነበረ ከኛው ጋር አብረው አለቀሱ። ተማሪዎቹም ነገሩ ስላስገረማቸው ትምህርታቸውን ትተው እኛኑ ይመለከቱ ነበር። ወዲያው አስተምሐሪዬ አባቴን ወደ ቤት እንዲገባ አደረጉና ለብቻቸው ጥቂት ከተነጋገሩ በኋላ ምሳ ተጋበዙ ።

ከምሳ በኋላም አባቴና አስተምሐሪዬ ለብቻ ሆነው ንግግራቸውን ቀጠሉ።

እኔም ተጠራሁና እዜያው እንደቆምኩ አባቴ አስተምሐሪዬን “መርቀው ይስጡኝ እንጅ እርስዎ እንደዚህ እያዘኑ ብወስደው እግዚአብሔርም አይወድ” አሏቸው። “እኔ አልወለድኩት፣ የወለዱት እርስዎ፣ ከነተረቱ የወለደ ቢነዳ አያስጥል የረዳ ይባላል” አሉና አስተምሐሪዬ ያለቅሱ ጀመር።

በዚያን ጊዜ አባቴ እንደዚህ እያዘኑ ብወስደው መልካም አይደለም እንዲያውም ካገሬ እሱን ፍለጋ ስመጣ ጊዳ ከሚባል አገር ስንደርስ የሱ ታላቅ ወንድም ሙሉጌታ ወልደ ዮሐንስ የተባለው ልጅ ታሞብኝ በበቅሎ ጥቂት ከተጓዘ በኋላ ስለጠናበት መንደር ለምኜ አስተኝቼው መጥቻለሁ። አለፈቃድዎ ወስጄ ይህም አንድ ነገር ቢደርስበት ታላቅ ፀፀት ይሆንብኛል ብሎ ነገራቸው።

ከዚህ በኋላ ተስማሙና አባቴም መርቄ እሰጥዎታለሁ ስላላቸው አስተምሐሪዬ እጅግ ተደስተው ስለታመመው ልጅዎ እግዚአብሔር እንዲምረው ፀሎት እናደርጋለን አሉና አሳርገው ተሰነባበቱ። እኔም አባቴን እስከገዳሙ አፋፍ ድረስ በቅሏቸውን እየሳብኩ ሸኝቼ ተመለስኩ ከዚህ በኋላም ትምህርቴን ጠንክሬ በመቀጠል ይህንንም አስተመሐሪየን በቅንነት በማገልገል አንዳች ችግር ሳይደርስብኝ አንድ ዓመት ካለፈኝ በኋላ አስተማሪ አባ ገብረ ሚካኤል በጠና ታመሙ። በቅርብ ሆኜ የማስታምማቸውና የምረዳቸው እኔ ብቻ ነበርኩ። ሌላ ዘመድ አልነበረም። ወይዘሮ ጽጌና የሥዩም እናት ወይዘሮ አሰገደች በየዕለቱ እየመጡ ይጠይቋቸው ነበር።

ሕመማቸው እየጠናባችው ስለሄደ በመጨረሻ ብዙ ታመው አረፉ። የሳቸውም መሞት ለኔና ለተማሪዎቹ ታላቅ ጉዳትና ሐዘን ሆነብን። ያላቸውን ልብስና ማናቸውም ዕቃም ሆነ መጽሐፍ ገዳሙ ስለወሰደው ድርጎውም ስለተቋረጠ ተማሪዎቹም ተበታተኑ። እኔንም አጠገባቸው /ባንድ ግቢ/ ጓደኛቸው የነበሩ አባ ወልደ ሩፋኤል የተባሉ መነኩሴ አይዞህ ሌላ ትምህርት ቤት ፈልገን ትቀጥላለህ እያሉ ያጽናኑኝ ጀመር። እንዲሁም አባ ገብረ ሚካኤል የሚባሉ የቤተክርስቲያኑ ሊቀ ዲያቆን ትልቅ ሰው ከጐረቤታችን የነበሩ ስለሚያውቁኝ፣ እኔ ዘንድ ተቀመጥ፣ ትምህርትንም አቶ ወልደ ጻድቅ የሚባሉ በጣም ጥሩ አስተመሐሪ አሉና እሳቸው ዘንድ ትማራለህ በማለት ነገሩኝ። እኔም እሺ ብዬ እሳቸው ዘንድ ገባሁ።

ወዲያውም ከአቶ ወልደ ጻድቅ ዘንድ ወስደው አገጣጠሙኝ። እውነትም በጣም ጥሩ ጉበዝ ኃይለኛ አስተመሐሪ ናቸው። የጉብዝናቸውና የኃይለኝነታቸው ዝና የታወቀ ነው። ከነስማቸው አቶ ወልደ ጻድቅ በመባል ፋንታ "አዝብጤ" የሚባል ሥም አውጥተውላቸው ነበር።

ማታ ማታም ቅዳሴና ሌላም ዜማ ከሚጠናበት ትምህርት ቤት አስገቡኝ። ቀን ንባብ ከምማርበት ከአቶ ወልደ ጻድቅ ዘንድ ብዙ የታላላቅ መኳንንት ልጆች ይማራሉ። ከነዚህም አንዱ እንዳልካቸው መኮንን ነበር። ከነሱ በትምህርት እኔ ስለምበልጣቸው እንዳልካቸውን እህቱንና እንዲሁም አስቴር ካሣ የተባለች የፊታውራሪ ካሳ ወልደ ጊዮርጊስን ልጅ አስተመሐሪዬ እያዘዙኝ አስተምራቸው ነበር።

በዚሁ ጊዜ የነበርኩባቸው አባ ገብረ ሚካኤል ገዳም የሚሰጣቸውን ድርጎና በዕልቅናቸው የሚያኙትን የተለየ አበል ሁሉ እኔ ኃላፊ ሆኜ እንድቀበል አድርገውኝ ነበር። ልብስም በደንብ ስለሚሰጡኝ ችግር አልነበረብኝም።

# የጣሊያን ጦር በደብረ ሊባኖስ

በትምህርት በኩል የደረስኩበትም ደረጃ መጀመሪያ ዳዊት በሚገባ እየከለስኩ ካጠናቀቅሁ በኋላ ንባብና የቃል ትምህርት ቀጠልኩ። ከዚያም ዜማ ጀምሬ ትምህርቱ ደስ ብሎኝ በማካሄድ ላይ እንዳለሁ የኢጣሊያኖች የጦር መሪ ሆኖ አዲስ አበባ በሚገኘው በግራሲያኒ ላይ ኢጣሊያኖችን ተቀዋሚ በሆኑ ኢትዮጵያውያኖች እጅ የካቲት 12 ቀን 1929 ዓ.ም ቦምብ ተጥሎበት ቆስሎ ኖሮ ወሬውን ሰማን። እነዚህም በግራሲያኑ ላይ ቦምብ የጣሉ ሁለት ሰዎች ደብረ ሊባኖስ ድንገት መጥተው አባ ሐና ቤት አድረገው ገዳሙም ጋብዟቸው ነበር። የመጡትም በኦቶሞቢል እንደነበረ ተመልክተናል። እኔም ራሴ በደንብ አይቻለሁ።

በዚሁም በተጣለው የቦምብ አደጋ ምክንያት የአዲስ አበባን ሕዝብ ከፈጀ በኋላ የኢጣሊያን ጦር ሠራዊት በድንገት ወደ ደብረ ሊባኖስ መጥቶ ስለከበበን በገዳሙ ውስጥ የሚኖረው አብዛኛው ሕዝብ ቀደም ብሎ ወሬውን በመስማት በየጫካው ሸሽቶ ስለገባ እንዳሰበው ሰውን በብዛት ሳያገኘው ቀረ።

በዚሁ ጊዜ የተገኙትን መነኮሳት፣ ደብተሮችን፣ ተማሪዎችና ሌላውንም ባካባቢ ነዋሪ የሆነውን ሕዝብ ሁሉ ሰብስቦ የኢጣሊያን መንግሥት እናንተን ሊረዳ ነው የመጣው በማለት ከሰበከ በኋላ ለገዳሙ መርጃ ይሁን ሲል ብዙ ገንዘብ ለሹማምንቶችም የተለየ ሽልማት ሰጥቶ አንድም ሰው ሳይነካ ተመልሶ ሄደ።

ከዚያን ጊዜ ወዲህ አልፎ አልፎ የኢጣሊያን ሹማምንቶች ወደ ገዳሙ እየመጡ ተጨማሪ ገንዘብ በመስጠት አዲስ ሹም በመሾም ሲያረሳሱ ቆዩና በሦስተኛው ወር የአቡነ ተክለ ሃይማኖት ትልቅ በዓል በሚከበርበት በግንቦት 12 ቀን 1929 ዓ.ም ብዙ ሕዝብ ከያለበት ከአራቱ አገር ሳይቀር ለክብረ በዓል የሚሰበሰብበት ስለሆነ ይኸንኑ ጊዜ ጠብቆ በዓሉ በሚከበርበት ዋዜ ካህናቱና እንዲሁም ሕዝቡ በቤተክርስቲያኑ ውስጥና ግቢ በአካባቢው ጭምር እንደተሰበሰበ በዓሉን ለማክበር አስመሰሉና የኢጣሊያን የጦር ሹማምንቶች ሳይታሰብ ከተፍ አሉ። ወዲያውኑ እነሱ የሾሟቸውን የገዳሙን ጠባቂና የምርፋቁን ኃላፊ መጋቢውንም ጭምር አስጠርተው "ዛሬ የመጣነው የኢጣሊያን መንግሥት እዚህ ካለው ሕዝብ

ልብስና ገንዘብ እንድንሰጥ አዞን ስለሆነ በየቤቱ ያለው ሕዝብ ሁሉ እዚሁ እቤተ ክርስቲያኑ ቅጥር ግቢ በሙሉ እንዲሰበሰብ አድርጉ" ብሎ አዘዘ።

ወዲያውኑ በየትምህርት ቤቱና በየመቃብር ቤቱ ያሉት ደካሞች ሳይቀሩ ተጠሩና ሲበሰበሰቡ ወዲያው መጠን የሌለው የጦር ወታደር ገዳሙንና በተለይም ቤተክርስቲያኑን ካፋፍ መከስ ቀበሌውን በሙሉ ባንድ ጊዜ በመትረየስ ከበበው። ከዚያ በኋላ ማንም ሰው ካለበት ስፍራ እንዳይነቃነቅ አስጠንቅቆ ወደ ገዳሙና ወደ ቤተክርስቲያኑ የሚገባ እንጂ የሚወጣውን ከለከሉ። ወዲያው በየክፍሉ በኢጣሊያንኛ መኪና ፀሐፊዎች ተመደቡና ማንኛውም ሰው ሥሙን ከነአባቱ የተወለደበት አገር ዘሩና የመጣበት ጊዜ ጭምር መጻፍ ተጀመረ። ሌሊቱን ሁሉ ሳያቋርጥ ሲሠሩ አደሩና በማዕግስቱም እስከ ስድስት ሰዓት ድረስ ሠርተው ወዲያውኑ የወታደር ካሚዬን አሰልፈው መነኩሳቱንና ደብተራውን በቅድሚያ አሳፍረው ቀጥሎም ተማሪዎቹን በሌላ መኪና አሳፈሯቸው። አንዳንዱን ከእሩቅ አገር ለጠበልና ለበዓሉ ንግሥ የመጣውን እየመረመሩ ይለቁ ነበር። ከቤት መውጣት የማይችሉትን ደካሞችና ዓይነ-ስውሮች እንዲሁም ልዩ ልዩ በሽተኞች እዚያው አሉበት ፈጇቸው እየተባለ ሲወራ ሰማን።

ከዚህ በኋላ መነኩሳቱና ደብተሮቹ የተሳፈሩበት መኪና ብዛት ስፍራውን አጣቦት ስለነበር ተንቀሳቅሶ ጉዞውን ጀመረ። ካንድ ሰዓት በኋላ ተማሪዎቹ የተሳፈሩበትም ካሚዬን ተከትሎ ከገዳሙ አምስት ኪሎ ሜትር ከሚርቅ ጫጋል ከሚባል ስፍራ አቆመ። እዚያም ሁለት ሰዓት በላይ ከቆዩ በኋላ ከቀደም ብሎ የተሳፈሩትን 650 የሚሆኑ መነኩሳትና ደብተሮች ወደ ፍቼ ከተማ አቅራቢያ አለተ ማርያም ከተባለው ስፍራ ወስዶ ወዲያውኑ በመትረየስ ፈጅቷቸው ኖሮ መጽሐፍቶቻቸውንና በደም የተለወሰ ካባና እንደጋቢ ያለ ልብሳቸውን እያመጣ ከፊታችን በተነው።

እኛም ማለቃቸውን ስለተረዳን ካሁን አሁን ይፈጁናል በማለት ስንጠባበቅ እስከ ምሽቱ 3 ሰዓት ቆይቶ ካሚዩኑ ጉዞውን ወደ አዲስ አበባ ቀጠለ። ሌሊቱን ሲሄድ አድሮ ሲነጋጋ ደብረ ብርሃን ከተማ ደረስን።

ከዚያም በአንድ የወታደር ሰፈር ውስጥ እንድንወርድ ተደረገና እንደገና ስማችንና ዕድሜአችን ይፃፍ ጀመር። ከ18 ዓመት በላይ ያለውን ለብቻ ከ18 ዓመት በታች ያለውን ለብቻ በማድረግ ከለየ በኋላ ከ18 ዓመት

በታች ያለነው 32 ቁጥር ስንደርስ የቀረውን ጽፎ ሳይጨርስ በቃ በቃ ብሎ ሌሎቹን ተማሪዎች እዚያው አስቀረ። ወደ ደብረ ብርሃን የተወሰድነው ተማሪዎች 215 ስለነበርን 32ቱን ለብቻ ወስዶ ደብረ ብርሃን ሥላሴ ቤተክርስቲያን በግንቡ ሥር 8 ድንኳን ተክሎ አራት አራታችንን ባንድ ድንኳን ውስጥ አስገባን። እስከዚያ ሰዓት ድረስ የሚጠብቁን ወታደሮች ካራቢኔሬ የተባሉት ሲሆን ከዚያ በኋላ ያር ባንዳ ወታደር ተቀየረና እንዲጠብቁን ተደረገ።

በዚሁ ቀን ከሰዓት በኋላ እዚያ የቀሩትን ጓደኞቻችንን ተማሪዎች በሙሉ ፈጅቷቸው ኖሮ ያንዳንዶቹን ልብስና መጽሐፍ እያመጡ አሳዩን። ከከተማው ወጣ ብሎ በሚገኝ ጉድጓዳ ስፍራ ላይ በመትረየስ መደብደባቸውንም የሚጠብቁን ወታደሮች ነገሩን።

ደብረ ብርሃን 6 ወር ከታሠርን በኋላ በኅዳር ወር 1930 ዓ.ም በድንገት ካራቢኔሬዎች መጥተው ከበቡን። እኛም ጓደኞቻችንን የፈጁ ወታደሮች በመምጣታቸው በጣም ደነገጥን። በዚሁ ጊዜ እኛን ትምህርት የሚያስተምሩ ለጦር ሠራዊቱም መንፈሳዊ ምክር የሚሰጡና የሚባርኩ እንደ ጳጳስ የተከበሩ ትልቅ መነኩሴ ነበሩና እነዚህን ልጆች ሊፈጇቸው ነው ብለው ቢነግሯቸው ሰውዬው በኢጣሊያ የፖለቲካ ሰዎችና ባለሥልጣኖች ዘንድ የታወቁ ስለሆነ ወዲያውኑ በሬዲዮ መገናኛ አስምተው ከሞት እንድንድንና ወደ ሞቃዲሾ ሔደን እንድንታሰር አደረጉ። ደብረ ብርሃን 6 ወር በታሰርንበት ጊዜ ሁለት ልጆች በሕመም ምክንያት ሲሞቱ የቀረነው 30 ብቻ ነበርን። የሚጠብቁን ያገር ባንዳ ወታደሮች በሚቀያየሩበት ጊዜ ካገራችን ከቡልጋ የተቀጠሩ የማውቃቸው ወታደሮች ስላገኘሁ ወዲያኑ ለዘመዶቼ ልከውባቸው ኖሮ አባትና እናቴ ወንድሞቼና ዘመዶቼ ሁሉ መጥተው ከኢጣሊያኖች ሹማምንቶች እያስፈቀዱ እታስረክቡት ጠየቁኝ። እናቴም እዚያው ደብረ ብርሃን ተቀምጣ ሁኔታውን በመጠባበቅ በየሶስት ቀኑ እየመጣች ትጠይቀኝ ነበር። እንድንሞት የተደረገው ውሳኔ ወደ እሥራት ከተለወጠልን በኋላ በዚሁ ዕለት ሌሊቱን አሳፍረው አዲስ አበባ ነፋስ ስልክ የእሥረኞች ካምፕ ከሆነው ስፍራ አስገቡን። ጧት ሲነጋ ብንመለከት የአዲስ አበባ መኳንንትና ሴት ወይዘሮ ተሰብስቦ የታሰረበት ስፍራ መሆኑን አየን። እሥረኞችም እጅግ ብዙ ነበሩ። ከደብረ ሊባኖስ አካባቢ ካሉትም ነዋሪዎች እየተያዙ እዚሁ ታስረው አገኘናቸው።

የትምህርት ቤት ጓደኛዬ የነበረው ሥዩም ገብረ እግዚአብሔርም ከነእናቱ ነበር። አባቱ ግን እዚያው ደብረ ሊባኖስ በተያዝን ጊዜ ከደብተሮቹ ጋር አብረው ተፈጅተዋል።

ነፋስ ስልክ ወህኒ ቤት በኢጣሊያን የነጭ ወታደሮች እየተጠበቅን 15 ቀን ከቆየን በኋላ እዚያ ካለው እሥረኛ የፈለጉትን ፈጅተው የቀረውን ወደ ሞቃዲሾ ወሰዱን። በምንጓዝበት ጊዜ ሁሉ ሕዝቡ እንዳያይ እንደ ደብረ ዘይት፣ ናዝሬት፣ ድሬዳዋና ሐረር ያሉትን ከተሞች የምናቋርጠው ሌሊት ሌሊት ነበር። ጅጅጋ ስንደርስ ግን የሱማሌ ወታደሮች ስለተረከቡን ከዚያ በኋላ ከተማ የምናቋርጠው በማናቸውም ሰዓት ነው። በዚህ ዓይነት ተጉዘን ከአዲስ አበባ በተነሳን በ13ኛ ቀን ሞቃዲሾ ገባን። እዚያም በጣም ብዙ የሆኑ ኢትዮጵያውያን ወንዶችና ሴቶች እስረኞች አገኘን።

የወንዶቹና የሴቶቹ እስር ቤት የተለያየ ስለሆነ ከባሕሩ ወደብ ለመታጠብም ሆነ ለመናፈስ ስንወጣ እንተያያለን እንጂ ተቀራርበን አንነጋገርም። ሞቃዲሾ በነበርን ጊዜ ወንዶቹ ከወህኒ ቤቱ ውጭም ሆነ ግቢ የሥራ ፕሮግራም አለን። ይህም በቢሮ ሠራተኛነት፣ በእንጨት ቆረጣና በቤት ሥራ ይህን በመሳሰለው ነው። ከዚህም በቀር ማታ ማታ ሁልጊዜ እሥረኛው ሁሉ በየአቅራቢያው እየሰበሰበ ምሕላና እግዚኦታ ያደርግ ነበር። ይኸንንም ኢጣሊያኖቹ አይከለክሉም።

የምግብና የልብስ ችግር የለም ሆኖም ብዙውን እሥረኛ በሽታ ስላጠቃው ሆስፒታልም ቢኖር እዚያው እየሞተ የቀረው እጅግ ብዙ ነው፣ ሲሞትም እሥረኛው ሁሉ ተሰብስቦ ዘመድ ያለውም እያለቀሰ እዚያው ከባሕሩ ዳር አሸዋ ላይ ይቀብራል፣ እኔም በጣም ታምሜ በእግዚብሔር ቸርነት ዳንኩ፣ በሕይወቴ እንዲያ ያለ ጠንካራ ሕመም አጋጥሞኝ አያውቅም።

ከሠካሳዎቹ ተማሪዎች ውስጥ ገና ስንሄድ ኦጋዴን ላይ ዘውዱ ወንድሙ የተባለ በጣም ጥሩ ልጅ ሲሞትብን ሞቃዲሾ ከኛ በኩል የሞተ የለም።

ከእሥረኞቹ ውስጥ በየጊዜው ምሕረት እየተደረገላቸው የሚለቀቅ ነበር። እኛም አቡነ አብረሃም አስምረዋችዋል ስለተባለ በ6ኛው ወር እንድንመለስ ተደረገ። ከኛም ጋር ምሕረት የተረገላቸው ብዙ ሰዎች ነበሩ።

ወደ አዲስ አበባ እንደመጣን ፊት ከነበርንበት ነፋስ ስልክ ወህኒ ቤት አገቡንና

ከዚያ ወደምንሄድበት በታተኑን። እኛን ከደብረ ሊባኖስ የተያዝነውን ልጆች በተለይ አሳፍረው እዚያው እገዳሙ ወሰዱን።

እዚያ እንደደረስን ጣሊያን የሾማቸው የገዳሙ መምህር ተጠሩና እነዚህን ልጆች የካካቸው የኢጣሊያን መንግሥት ነው። ቀለብና ደመወዝ ልብስም ይሰጣቸዋልና እዚሁ እየተማሩ ቤተክርስቲያን ያገልግሉ ብሎ አስረከበን። ለያንዳንዳችንም ልብስና በቂ ገንዘብ ተሰጠን። ሆኖም መጀመሪያ የተያዝንበትን ስፍራ ስናይና የጓደኞቻችንን የግፍ አሟሟት ስናስበው የምናየውና የምንበላው ሁሉ የደም ስሜት ስላሳደረብን እዚያ ለመቀመጥ ፈጽሞ አልፈቀድንም። ሁላችንም በዚሁ ሐሳብ ከተነጋገርን በኋላ በየትውልድ አገራችን ለመበታተን ተስማማን።

ጣሊያኖቹ ደብረ ሊባኖስ አድርሰውን በሄዱ ማዕግስት የቀሩት ወደየፈለጉበት ቦታ ለመሄድ ሲዘጋጁ እኔም ታደሰ ከተባለ ጓደኛዬ ጋር ሆነን ወደ አዲስ አበባ ጉዞ ቀጠልን። የይለፍ ፈቃድ ስለሌለን የመጣነው በእግራችን ስለሆነ በሁለተኛው ቀን ገባን። አዲስ አበባ እንደደረስን በተቀበልነው ገንዘብ ልብሳችንን ገዛዛንና እሱም አገሩ አድአ ቃጅማ ጊዮርጊስ ስለነበረ ወደዚያ ሲሄድ እኔም ከቡልጋ የመጡ ሸንኩርት ነጋዴዎች ፈልጌ ከነሱ ጋር ወደአሬ ጉዞዬን ቀጥዬ መንገዳችን በእግር ስለሆነ በ2ተኛው ቀን ገባን። ከደብረ ብርሃን ከተወሰድን ወዲህ አባትና እናቴ ሌሎችም ዘመዶቼ ሁሉ ኢጣሊያኖች እኛንም የፈጁን መስሎአቸው ስለመኖራችን ተስፋ ቆርጠው ስለነበረ ሳይታሰብ ድንገት ወደ ዘመዶቼ በምጣቴ ታላቅ ደስታ ተደረገ። ስለፈንጠዝያውም ወንድሞቼ ጠመንጃ ይተኩሱ ነበር። እንዴት ሞተ የተባለ ሰው ተገኘ በማለት ሕዝቡ ሁሉ የእግዚአብሔርን ተዓምራታዊ ሥራ አደነቀ።

ከዚህ በኋላ አገር ቤት ጥቂት ጊዜ እንደተቀመጥኩ ጣሊያን የቡልጋን አርበኞች በመፈለግ የሕዝቡን ቤት በሙሉ እያቃጠለ ቦምብ እንደ በረዶ በማዝነም ሰውን ሲያሰቃይ ነበር። ታላቅ ወንድሜም ሙሉጌታ ወልደ ዮሐንስ ከአርበኞች ዘንድ ስለነበረ ከሌሎች ብዙ ሰዎች ጋር ተይዞ በመትረየስ ደበደቧቸው።

እኛም ሴቱ ሳይቀር ወደጫካ እየሸሸን አዳራችን ጭምር አዱር ውስጥ ነበር። አልፎ አልፎ ፀጥታው ረጋ ሲል አቶ ትርፌ የተባለ የፀሐፌ ትእዛዝ

ወደ መስቀል መሬት ኃላፊ ወረቀት እንድጽፍለት በየጊዜው እየጠየቀኝ እጽፍለት ነበር። እሱም አዲስ አበባ በመጡ ጊዜ በጽሕፈት ሥራ የሚረዳው መሆኔን ነግሮአቸው ጠይቀውና ይዘኸው ና ብለውት ኖሮ አዲስ አበባ እንድንሄድ ስለጠየቀኝ እኔም በዚያን ጊዜ የነበረው ያገር ቤት ኑሮ በኢጣሊያኖች ምክንያት አስቸጋሪ ስለበረ እሺ ብዬው አባቴን ተሰናብቼ አብረን መጣንና ከክቡር ጸሐፊ ትእዛዝ ወልደ መስቀል አገናኘኝ። አኳኋኔን አለባበሴ የከተማ ሰው ይመስል ስለበረ እሳቸውም በደስታ አነጋገሩኝና ባልደረባም ተሰጠኝ።

ወዲያው ለሙከራ አንዳንድ ወረቀት እንድጽፍ አደረጉኝ። የሥራዬንም ሁኔታ በታላቅ ማስተዋልና ዘዴ ይመለቱ ጀመር። በኋላም አቶ ትርፌ ወደ ቡልጋ በሚመለስበት ጊዜ እኔ እሳቸው ዘንድ እንድቀር ተደረገ።

ቀደም ብሎ በኢጣሊያኖች የደረሰብኝን መከራና ስቃይ በዝርዝር ስለገለጽኩላቸው በጣም አዘኑ። ከዚያ በኋላ ማንኛውንም ሥራ ቶሎ ስለለመድኩት ከፀሐፊነቱም ሌላ ለቤተሰቡ ሁሉ ኃላፊ አደረጉኝ። ወደ አዲስ አበባ ይዞኝ የመጣውም አቶ ትርፌ አገር ቤት እንደደረሰ በድንገት ታሞ መሞቱን ሰማን።

በዚሁ ጊዜ አባቴ እኔን ለማየት አዲስ አበባ መጥቶ ነበርና የቡልጋን መሬት እሱ ኃላፊ ሆኖ እንዲጠብቅላቸው አደራ ሰጡት። እኔም ሥራዬን እያሻሻልኩ ሳገለግል ክቡር ፀሐፊ ትእዛዝ ወልደመስቀል እንደ ልጆቻቸው አድርገው በመመልከት ይወዱኝ ይመርቁኝም ነበር። በዚህ ዓይነት ካጠገባቸው ሳልለይ በቅንነት እያገለገልኳቸው ከቆየሁ በኋላ ጠላት አገራችንን ለቆ ወጣ።

ወዲያው ጌቶች ፀሐፊ ትእዛዝ ወልደ መስቀል የሕዝቡን ጉዳይ እየተቀበሉ ለጃንሆይ በማቅረብና በማስፈፀም እንዲሠሩ በተሾሙ ጊዜ እኔም በዚሁ ክፍል ተመድቤ የባለጉዳዮችን ጥያቄ ባጭር ቃል እያዘጋጀሁ የርስትና የገንዘብ ዳረቡት መዝገብ እንድይዝ ተደረገ።

አባቴም በዚሁ ዓመት ሐምሌ 21 ቀን 1933 ዓ.ም ስላረፉ ለለቅሶ አገር ቤት ሄጄ ተመለስኩ።

## በመንግሥት ሥራ ላይ ያገለገልኩባቸው ክፍሎች

1ኛ/ ከ1933 ዓ.ም እስከ 1934 ዓ.ም በሕዝብ ጉዳይ ማጣሪያና ማቅረቢያ ጽ/ቤት የባለጉዳዮችን ጥያቄ ባጭር ቃል ማዘጋጀት፣ የርስትም ሆነ የገንዘብ ዳረጐት መዝገብ መያዝ፣

2ኛ/ በ1935 ዓ.ም ባገር ግዛት ሚኒስቴር በፀሐፊነት እንዲሁም በሸዋ ጠቅላይ ግዛት የመዝገብ ቤት አቋም ምክትል ኃላፊ፣

3ኛ/ ከ1936 እስከ 1940 ዓ.ም የሕግ መወሰኛ ምክር ቤት ፕሬዚዳንት ልዩ ጽሐፊ፣

4ኛ/ በ1941 ዓ.ም የነፃነት ማተሚያ ቤት ሥራ አስኪያጅ፣

5ኛ/ ከ1942 ዓ.ም እስከ 1967 ዓ.ም በርሻ ሚኒስቴር በልዩ ልዩ ክፍል በኃላፊነት፣ ይህም፡-

ሀ/ ከ1942 እስከ 1945 ዓ.ም በአምቦ ከፍተኛ እርሻ ትምሕርት ቤት አድሚኒስትሬተርነት፣

ለ/ ከ1946 እስከ 1950 ዓ.ም በከብት ርቢ መምሪያ ምክትል ዋና ዳሬክተርነት፣

ሐ/ ከ1950 እስከ 1960 ዓ.ም የሚኒስትሩ ልዩ ጸሐፊነት፣

መ/ ከ1960 እስከ 1967 ዓ.ም በደን ልማትና ጥበቃ መምሪያ በዲሬክተርነት፣

ከዚህ በላይ እንተገለፀው በጠቅላላው 34 ዓመት አገልግያለሁ።


ሞዐ አንበሳ ዘእምነገደ ይሁዳ ።
ቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴ
ሥዩመ እግዚአብሔር ንጉሠ ነገሥት ዘኢትዮጵያ ።

ይህን ደብዳቤ ለሚያዩ ሁሉ ሰላምታችን ይድረሳቸው ።
እንደ ንጉሠ ነገሥትነታችን በተከበረው የኢትዮጵያ፡የክብር፡
ኮከብ፡ እኛ እዘዝን የበላይ በሥልጣናችን፤
ለአጥላው፡ ወልዴ፡ ዮሐንስ፡

ይህንኑ የተከበረውን የኢትዮጵያ፡የክብር፡ኮከብ፡የመኮንን፡
እኛ የሰጠነ መኮንና
ለማስከበር የተገባና የሚገባው ...

ለአጥላው፡ ወልዴ፡ ዮሐንስ፡

የተከበረውን የኢትዮጵያ፡የክብር፡ኮከብ እኛ
ሰጥተናል ።
ይህንንም የተከበረውን ሽልማት
በተሸለሙ የሚሰጣቸውን መብቶችንም ክብር ለአጥላው፡
ወ፡ዮሐንስ፡ ... ሙሉ ሙሉነትና ፈቃድ ሰጥተናል ።
... ዘመን ...
... የኢትዮጵያ ... ዘመን
... ።

## ስለ አገልግሎቴም መታሰቢያ

1ኛ/ የኢትዮጵያ የክብር ኮከብ የመኮንን ደረጃ

2ኛ/ የኢትዮጵያ የክብር ኮከብ የፈረሰኛ ደረጃ - ሊሻን ተሰጥቶኛል።

## ስለ ልደትና ጋብቻ አጭር ማስታወሻ

1ኛ/ አጥካው ወልደ ዮሐንስ በ1912 ዓ.ም ሰኔ 30 ቀን ተወለደ፣

2ኛ/ ሐመረ ገብረ ጻድቅ በ1926 ዓ.ም የካቲት 16 ቀን ተወለደች፣

3ኛ/ የአጥካውና የሐመረ በቁርባን የተክሊል ጋብቻ በ1940 ዓ.ም የካቲት 7 ቀን አዲስ አበባ ገብርኤል ቤተክርስቲያን ተፈፀመ።

## የልጆች ልደትና የትምህርት ደረጃ

1. ፍሥሐ አጥካው - በዚህ ዓመት ማለትም በ1967 ዓ.ም. የማስትሬት ዲግሪውን ያገኛል።
2. ፀሐይ አጥካው - በ1968 ዓ.ም የባችለር ዲግሪዋን ትቀበላለች።
3. ሠናይት አጥካው - በ1967 ዓ.ም በዩኒቨርሲቲ የመጀመሪያ ዓመት ተማሪ።
4. አማከለች አጥካው - በ1967 ዓ.ም በዩኒቨርሲቲ የ2ኛ ዓመት ተማሪ።
5. ደምሰው አጥካው - በ1967 ዓ.ም የ12ኛ ክፍል ተማሪ።
6. እጅግ አየሁ አጥካው - በ1967 ዓ.ም. የ10ኛ ክፍል ተማሪ።
7. ዮሐንስ አጥካው - በ1967 ዓ.ም የ9ኛ ክፍል ተማሪ።
8. ሥምረት አጥካው - በ1967 ዓ.ም የ8ኛ ክፍል ተማሪ።

እግዚአብሔር በቸርነቱ ባርኮ ቀድሶ የሰጠን ልጆች ከዚህ በላይ ስማቸው የተጠቀሱት ሲሆኑ፣ እነሱም በጤና - በትምህርት፣ የተሟላ አቋም አላቸው።

በዚህም ምክንያት እኛ ወላጆች የሚሰማን የመንፈስ ደስታና የምናቀርበው የእግዚአብሔር ምስጋና መጠን የሌለው ሆኖ ይገኛል። በመንፈሳዊም ሆነ በሥጋዊ አስተዳደር ትምህርት የቱን ያህል እንደሚጠቅም በመገንዘብ እኔ አዲስ አበባ እስራ ላይ ከነበርኩበት ዘመን ጀምሮ በየጊዜው ወደኔ ዘንድ እየመጡ በማደግ የትምህርት ዕድል ያጋጠማቸው ወንድሞቼ እህቶቼና ዘመዶቼ ከዚህ ቀጥሎ የሚገኙት ናቸው።

1. ኃይለ መስቀል ወልደ ዮሐንስ - ትምህርቱን ከተከታተለ በኋላ አቋርጦ ሥራ የያዘ።
2. ከገሰ ወልደ ዮሐንስ - ትምህርቱን በሚገባ አጠናቆ የዶክተሬት ማዕረግ አገኘ።
3. ደብራሁ ወልደ ዮሐንስ - ትምህርት ጀምራ በትዳር ምክንያት ያቋረጠች።
4. ውቤ ማነህ - 12ኛ ክፍል ድረስ አጠናቆ ሥራ የያዘ።
5. ውድነሽ ይርጋ - የኤሌሜንታሪ ትምህርት ተከታትላ ሥራ የያዘች።
6. አስካለ ኃይለ ማርያም - የኤሌሜንታሪ ትምህርት ተከታትላ በሥራና በትዳር ምክንያት ያቋረጠች።
7. አከሊሉ በቀለ - የኤሌሜንታሪ ትምህርቱን ተከታትሎ ሥራ የያዘ።
8. ማንጉዳይሽ ታደሰ - የኤሌሜንታሪ ትምህርት ተከታትላ በትዳርና በሥራ ምክንያት ያቋረጠች።
9. ምንዳ ምንደሲል - ትምህርት ጀምሮ በማቋረጥ ወደገር ቤት የተመለሰ።
10. ተረፈ ግካግሌ - ትምህርት ጀምሮ በማቋረጥ ወደገር ቤት የተመለሰ

ልዕልናው የማይወሰን ፈጣሪያችን በያንዳንዳችን ላይ የሚያደርገው ታሪካዊና ቸርነት የተመላበት ሥራ በሰው አንደበት ተነግሮ አያልቅም። ውለታው የሚከፈል ቢሆን በምን ዓይነት ሊታሰብና ሊገመት ይችላል? - የኛ አቅም እንዲሁም በደፈናው፣ ለመንግሥትህ ሕልፈት፣ ለሥልጣንህ ሽረት፣ ለቸርነትህ ወሰን - የሌለብህ ኃያልና ዘለዓለማዊ አምላክ እያሉ ማመስገን ብቻ ስለሆነ ሌላ የምንሰጠው ዋጋ የምንከፍለው ውለታ የለም።

ማንኛውንም ሥራ አነሳስቶ ለሚያስጀምር፣ አስጀምሮ ለሚያስፈፅም አምላክ ክብር ምስጋና ይድረሰው። አሜን

## በብሔራዊ ቋንቋ በአማርኛ ፊደል ስለሚሰጠው ትምህርት አቋምና ደረጃ ከዚህ ቀጥሎ በመጠኑ ተጽፎአል።

ረጅም ለሆነ ዘመናት የቆየው የኢትዮጵያ የትምህርት አቋም መሠረቱ ግዕዝ ሆኖ ቋንቋው አማርኛ ሲሆን ግዕዝ በትምህርት የሚገኝ ነው። የኢትዮጵያ ፊደል ቀደም ብሎ በነበረው ዘመን በሙሉ ግዕዝ ሲሆን አማርኛ ብሔራዊ ቋንቋ ሆኖ ከተስፋፋ በኋላ ለአማርኛ አነጋገር ተስማሚ የሆኑ ተጨማሪ ፊደሎች ከዓረብኛ

ተተርጉመው በመግባት በአገልግሎት ላይ ይገኛሉ።

እነዚህም ለምሳሌ ሸ፣ ቸ፣ ኘ፣ ኸ፣ ዠ፣ ጀ፣ ጨ በሚሉት በቅፅል የሚገቡ ናቸው። እነዚህ ከመግባታቸው ቀደም ብሎ ማናቸውም ጽሑፍ የሚከናወነው በግዕዝ ነበር። አማርኛ ብሔራዊ ቋንቋነቱ ከተረጋገጠ በኋላ ግዕዝ እየተዳከመ ሄደ። አማርኛ ተስፋፍቶ ይገኛል። ሆኖም ኢትዮጵያ ልዩ ልዩ ቋንቋ ተናጋሪ ጎሳዎች የሚገኙባት አገር እንደመሆንዋ አማርኛ የማይናገሩ ብዙ ጎሳዎች ይገኛሉ።

ለምሳሌ ከብዙ በጥቂቱ ኦሮሚኛ፣ ትግሪኛ፣ ጉራጌ፣ አገው፣ ሶማሌ፣ አዳል፣ ወላሞ፣ ጉደላ፣ ከፋ፣ ኬሎ፣ ሲሚራ፣ ኩልሶ፣ ባኩና ሌላም ይህን የመሳሰሉ ብዙ አሉ። እነዚህም ቢሆኑ የሚጠቀሙበት በአማርኛ ፊደል እንጂ ሌላ ፊደል የላቸውም።

የኢትዮጵያ ታሪክ ከውጭ አገር ቋንቋ በተለይም ከዓረብኛ የተገኙት የታሪክ መጽሐፍ በየገዳማቱና በታሪክ ነገሥታትም የተጻፉት በግዕዝ ቋንቋ እንደነበር አዋቂዎች ይናገራሉ። ቀደም ብሎ በነበረውም ዘመን ትምህርት እንዲስፋፋ ከማድረግ ይልቅ የየመኳንንቱና የየባላባቱ ልጅ በቤተ መንግሥት አስተዳደር እየተመለመለ የሲቪልም ሆነ የወታደርነት ሹመትና ማዕረግ እንዲያገኝ ሌላው ሕዝብ ደግሞ የየሻለቃው ጭፍራ ሆኖ ባገር አገዛዝና በወታደርነት እንዲኖር ማድረግ የመንግሥቱ አሰራር ልማድ /ፖሊሲ/ ስለመሆኑም ይነገራል።

ትምህርት ለመማር የተፈጥሮው ፍላጎት የገፋፋው በገዛ ፈቃዱ ከወላጆቹ ቤት በመኰብለል ቤተ ክርስቲያን ወዳለበት ሄዶ ፊደል በመቁጠርና ንባብ በመማር ጠንከር ብሎም የቀጠለው ዜማ ወይም ቅኔ ትምህርት ቤት በመግባት ይማራል እንጂ መንግሥት ወይም ሕዝቡ ያቋቋመው ትምህርት ቤት አያገኝም። ምግቡንም በየቤተ ክርስቲያኑ ተጠግቶ በማገልገልና አብዛኛውንም ጊዜ ሕዝብ በሰፈረበት መንደር እየዞረ በመለመን የሚያገኘውን ተስፋ አድርጎ በመኖር ነው።

ሀብታም የሆኑ አንዳንዶቹም ለልጆቻቸው የንባብ አስተማሐሪ እቤታቸው በመቅጠር ወይም ስንቅ እየሰጡ ትምህርት ካለበት ሥፍራ በመላክ ይማራሉ። ሆኖም አብዛኛው ተማሪ ሊማር የሚችለው ለምኖ በመብላት ስለሆነ ይህ እንደ ነውር ሆኖ አይቆጠርም። ለትምህርት ቤቱ ዋጋ አይጠየቅም ነፃ ነው። ለአስተመሐሪዎቹ ግን አንዳንድ ጊዜ የጉልበት አገልግሎት ይበረከታል።

የትምህርቱም ደረጃ የሐዲስና የብሉያት መጻሕፍት ትርጓሜ መምህርነት ድረስ የሚወስደው ትምህርት እንደ ፕሮፌሰርነት የሚቆጠር ነው። በጣም ታላቅ ትምህርት ነው። ይኸንንም አጠናቆ ለመመረቅ እስከ አርባ ዓመት ይፈጃል።

በኢትዮጵያ የዚህ ዓይነት ከፍተኛ ትምህርት የሚሰጥባቸው አገሮች በቅኔ በኩል በጎጃም ዋሸራና በጌምድርም ዋድላና ደላንታ በሚባሉት አገር ውስጥ በዜማ በኩል ደግሞ አብዛኛውን ጊዜ በበጌምድርና ሰሜን ክፍለ አገር በተለይም ቤተልሔም የተባለው የድጓ ዜማ መመረቂያ ስፍራ ስለሆነ የዜማ ትምህርት የሚጠናቀቀው በዚሁ በሰሜን ክፍለ አገር ነው።

የመጽሐፍት ትርጓሜ ትምህርት የሚገኝባቸው ክፍለ አገሮች፣ ጎጃም፣ በጌምድር፣ ሰሜን ወሎ፣ ትግሬና እንዲሁም ሸዋ ጭምር ናቸው።

ከፍተኛ ትምህርት የተማሩ ሰዎች የሚሰጡት ጥቅም በቤተ ክርስቲያን አስተዳዳሪነት፣ በአስተምሐሪነት፣ በቤተ መንግሥትም በኩል የሕግ መጽሐፍትን በመተርጎም ሥራ ላይ በማዋል እያቀናበሩና እያስረዱ ይሰራሉ።

ለምሳሌ እንደ ፍትሐ ነገሥት ያሉትን የወንጀልም ሆነ የፍትሐ-ብሔር ጉዳይ አጣምረው የያዙትን እንደያግባባቸው ከግዕዝ ወደ አማርኛ ከመተርጎም በየነገሥታቱና በየመሳፍንቱ ዘንድ ለማስረዳትና ትክክለኛውን ዓላማ እንዳይስት በማድረግ ያገለግላሉ። ካገልግሎታቸው ርስት ጉልትና ገንዘብ ይሰጣቸዋል።

በተማሪውና በአስተማሪው መካከል ያለው ልዩነት በጣም ሰፊ እንደነበረ በአፈጻጸሙ ለመረዳት ይቻላል። የተማሩት ባልተማረው ላይ ጉዳት ይፈጹሙበት ነበር። ለምሳሌ አንድ አባት ብዙ ልጆች ትቶ በሞትና ልጆቹ የሚያድጉበት ከብት እህል ቢኖረውም በልጆቹ ማሳደጊያ ተዝካር መውጣት አለበት በማለት እህሉንና ከብቶቹን ከልጆቹ አፍ በመንጠቅ ተዝካር አስደግሰው በመብላት አሳዳጊ አባት ካጡት ልጆች ርህራሄ አያደርጉም። በሽተኛውንም ወተት የጠጣህ እንደሆነ ትኮነናለህ ወተት ጠጥተህ ከምትድን መሞት አለብህ እያሉ ስለሚገዝቱት ሕዝቡም የተማሩትን ሰዎች ቃል አክብሮ በመስማት ብዙ ጉዳት ይደርስበት እንደነበረ ይነገራል። ከዚህም በተቀር በዓል በማብዛትና የሥራውን ጊዜ በማሳነስ በበዓል አትስሩ የሰራችሁ እንደሆነ የእግዚአብሄር ቁጣ /መዓት/ ይደርስባችኋል በማለት እያወገዙ ያስቸግሯቸው ነበር። ከቶውንም የቤተ ክህነቱ ክፍል በመንግሥቱ ዘንድ ተደማጭነት ያለው ስለሆነ የበዓል ሻሪ የተባለ ደንብ እንዲቋቋም አስደርገው ሰርቶ ነዋሪውን ሕዝብ እያስከሰሱ ቅጣት እንዲደርስበት ያስደርጉታል ይባላል።

በትምህርት ችሎታ ያለው የሹመት ደረጃና የማዕረግ ሥም በምንኩስናና በደብተርነት በኩል ልዩነት አላቸው። በምንኩስና ማዕረግ ያለው ከፍተኛው የሹመት ደረጃ ርዕሰ ሊቃነ ጳጳሳት ወፓትርያርክ፣ ሊቃነ ጳጳስ፣ ጳጳስ፣ ኤጴስ

ቆጳስ፣ ቆሞስ ሲሆን በደብተርነት ማዕረግ ያለው ደግሞ በቤተ ክርስቲያን አስተዳዳሪነት ሊቀ ሊቃውንት ንቡረ ዕድ፣ መላከ ገነት፣ መምህር ወይም አለቃ፣ ሊቀ ጠበብት፣ ርዕሰ ደብር፣ አጋፋሪ፣ ቀኝ ጌታ፣ ግራ ጌታ፣ ቄሰ ገበዝ፣ ሊቀ ዲያቆን እየተባለ የሚሰጥ ሹመትና ማዕረግ ነው።

ወላጆች ቀደም ብሎ በነበረው ዘመን ልጆቻቸውን ለማስተማር የነበራቸው ፍላጎት በጣም አነስተኛ ነበር። ምክንያቱም ከትምህርት ጥቅም ይልቅ በልማዱ ለሚጠቀሙበት ለእርሻና ለከብት ርቢ ሥራ ቅድሚያ ስለሚሰጡ ልጆቹ የርሻና የከብት እረኝነትን /ጥበቃን/ ሥራ ጠንክረው እንዲለምዱ ያደርጓቸዋል። የኑሮአቸውንም አቋም በዚሁ እንዲመሠርቱ እንጂ ወደ ትምህርት ቤት ሄደው እንዲማሩ አያደርጉም።

ሆኖም አንዳንዶቹ ልጆች በተፈጥሮአቸው የትምህርት ፍላጎት እያደረባቸው ከቤተሰቦቻቸው በመኮብለል ጠፍተው እየሄዱ ትምህርት በሚሰጥበት ስፍራ ይማራሉ።

ግብሩ የቤተክርስቲያን ማደሪያ የሆነ መሬት ያላቸው አንዳንዱ ሰዎች ወንድ ልጅ ሲወልዱ የቤተ ክርስቲያን ግብር በአገልግሎት እንዲገብርላቸው ለማድረግ የሚያስተምሩ አልፎ አልፎ ይገኛሉ። የካህን ልጅ ከሆነ ግን በአባቱ እግር ለመተካት ሲባል እንዲማር ያደርጉታል።

## ኢ.አ የካቲት 20 ቀን 1967

ለውድ ልጄ ፍሥሐ አጥላው፣ እንደምን ሰንብተሃል ጤናህን እንዴት ነው? እኛ ሁላችንም ካንተ ከማሰብና ከመናፈቅ በስተቀር በጣም ደህና ነን ቸር አምላክ ይመስገን። ባለፈው ጊዜ የጻፍክልኝ ደብዳቤ በኅዳር ወር መጀመሪያ ገደማ ደርሶኝ እስካሁን መልሱን ያልጻፍኩልህ የጠየቅኸኝን እስካዘጋጅ ድረስ ነበር። በደብዳቤህ እንደገለጽከው የጊዜ እጥረት ስላለብኝ በዕረፍት ጊዜ እያዘጋጀሁ ጨርሼ ይኸው አሁን ተጠናቀልኛል። ይህም እንዳሰብከው በኤዱኬሽን ለምትከታተለው ትምህርት ጥቂት ይረዳህ ይሆናል ብዬ አገምታለሁ። የነገሩም መነሻ የኔን የሕይወት ታሪክ በመዘርዘር፣ በኢትዮጵያ የብሔራዊ ትምህርት ሁኔታ (ቀደም ባለው ዘመን) የነበረውን በመጠኑ የሚያስረዳ ነው። የጀመርኩትን አዘጋጅቼ ስጨርስ እጽፍለታለሁ በማለት አስቤ ስለነበረ ምንም ጽሑፉ ተከታትሎ ቢደርስህ ይኸንኑ ለመግለጽ ዛሬ ልጽፍልህ ቻልኩሙ። ከሁሉም ደስ ያለኝ በራሴ ላይ የደረሰውን ማናቸውንም የኑሮ አቋምና የትምህርት ሁኔታ በዓይኑ ያየሁትን በጆሮዬ የሰማሁትን ከአባቶቻችንም የሰማሁትን እውነተኛ ነገር አዘጋጅቼ ባንተ በኩል ካሰብከው የሪሰርች ማሟያ ኪረዳህ በመቻሉ ነው። ይህም ካንድ ሰው ለምሳሌ ከእኔ ከአምሳ ዘመናት በላይ ባለ ጊዜ ያጋጠሙን ታሪክ ነክ የዕድሜ ጉዞ ለማስረዳትና ወደፊት ለልጆቼ የታሪክ ማስታወሻ ለማቆየት የሚችልበት ምክንያት ሲያጋጥመው እጅግ ከፍ ያለ የመንፈስ ደስታ እንደሚሰጠው ይሰማኛል። ከሁሉም ጽሑፉን በካሴት ካስቀረጽኩት በኋላ በሁለት ሳምንት ውስጥ እንዲደርስህ አደርጋለሁ። ካሴቱን ግን እዚህ አገር የመጣው ጓደኛህ ሲመለስ ከሱ እልክልሃለሁ። በተጨማሪም የአማርኛ መዝገበ ቃላት (ዲክሽነሪ) በጥሩ ሆኖ ስለታተመ እሱንም ልልክልህ አስቤአለሁ። ምናልባት ይጠቅምህ ይሆናል፣ ትንሽ ክብደት ይለው መጽሐፍ ነው።

ባለፈው ጊዜ የላክሁልህ ልዩ ልዩ ጋዜጣ የደረሰህ መሆኑን ገልጸህልኛል። ከዚያ ወዲህ በጣም ብዙ ዓይነት ለውጥ ተደርጓል። አንዳንዱን ሳትሰማው አትቀርም። ከ11ኛ ክፍል በላይ እስከ ኮሌጅ ያሉት ተማሪዎች ከነመምህሮቻቸው ወደ ገጠር እንዲሄዱና ዕድገት በኅብረት በተባለው ፕሮግራም እንዲመደቡ ተደርጓል። አብዛኛዎቹም ሄደዋል፣ ፀሐይ አማከለችና ደምሰውም ዘምተዋል። ምናልባት ጽፈውልህ ይሆናል። ለስንት ጊዜ እንደሆነ በደንብ አልተገለጸም። ፍሥሐ በደብዳቤህ እንደገለጽህልኝ የሚቀጥለውን ዲግሪህን በኤሌክትሮኒክ ኢንጂነሪንግ ቴክኖሎጂና በኤዱኬሽን ለመመረቅ ማሰብህንና በዚሁ የምትዘጋጅ መሆንህ ባለፈውም ብዙ ችግሮች እንደነበሩብህና አሁንም ሌሊት ሌሊት እየሠራህ በሳምንት 40 ሰዓታቶች በሥራ ላይ የምታሳልፍ ስለመሆኑ አረጋግጠህልኛል። ከዚህ ውጭ ሌላ የተሻለ ምርጫም እንደሌለህ አስረድተኸኛል። መቼም እግዚብሔር

ምንጊዜም ካንተ ጋር ስለሆነ ድካምም ቢኖርበት ይህን የመሰለ ዕድል ማግኘትህም ራሱ ከፍ ያለ ዋጋ ያለው ነው። ያንተ ጓደኞችና እህቶችህ ይህን የመሰለ ዕድል አጋጥሟቸው ትምህርታቸውን ሳያቋርጡ ለመቀጠል ቢችሉ ኖሮ የቱን ያህል ተፈላጊ ይመስልሃል። ስለዚህ አሁንም ጠንክረህ መሥራትህና መማርህ ካንተ ልዩ ክብርና ደስታ ታገኝበታለህ።

ከመሄድህ በፊት እዚሁ የነበረውን የትምህርት ውዝግብ ራስህ ስላምታውቀው ልጽፍልህ አያስፈልግም። ፀሐይ ባለፈው ዓመት የባችለር ዲግሪዋን ማግኛዋ ነበር። ያላገደች ትምህርት ሁለት ዓመት አልፋ በመጨረሻው ዘንድሮ ደግሞ ወደገጠር እንድትሄድ ተደረገ። ለሚመጣውም ዓመት ያለውን የትምህርት ማግኘት ጉዳይ ማወቅ አይቻልም፡ ፡ ስለዚህ እግዚአብሔርን እያመሰገንክ በሥራም እየደከምክ ትምህርትህን እስከ መጨረሻው ቀጥለህ ያሰብከውን ብታሟላ ደስ ይለኛል። ከተቻለ ለዶክትሬቱ ወደፊት ከ2 ዓመት ጊዜ የበለጠ አይወስድምና በርታ ጠንክር። አንተ ዘንድ ወደ ኢትዮጵያ የመጣው (አሜሪካዊውን) ጓደኛህን ምንም እኔ ባላገኘው በጣም ጥሩ ሰው መሆኑን ልጆቹ ነገሩኝ። ሲመለስ እንጋብዘውና ያጫውተናል በማለት እየጠበቀነው ነው። በሱ እጅ የላክህልን ልዩ ልዩ የስጦታ መታሰቢያ ደርሶናል፣ እግዚብሔር ይስጥልኝ። ልጆቹም መደሰታቸውን ሳይጽፉልህ አይቀሩም፣ ምንጊዜም ቸር አምላክ ካንተ ጋር ያልተለየ ስለሆነ ችግሩ የሚቃለልበትን ዕድል እሱ ባለቤቱ ያስብልሃል ብዬ አምናለሁ። ጠንክር፣ በርታ። አብዛኛውን ችግርና የኑሮ ልዩነት ተቋቁመህ አሸንፈሃል ወደፊትም ታሸንፋለህና አይዞህ እምነት በፈጣሪ ላይ ብቻ ይሁን። እንግዲህ እንዳልኩህ የተዘጋጀው (የሕይወት ታሪክ) ወረቀት በቅርብ ይደርስሃል። ሰውየውም መመለሻው ሳይቀርብ አይቀርም እስከዚያው ጻፍልን። እናትህ የናፍቆት ሰላምታ ታቀርባለች። ደግነቱ በቅርብ ስልክ ደውለህ ተገናኝተናል እንጂ በጣም ታስባለች ለሷ ብቻ ብዙ ሳይዘገይ ጻፍላት። በል እንግዲህ ደህና ሁን፣ እግዚአብሔር ይጠብቅህ።

ያንተው - አጥላው

አባባ፡-

በአሜሪካን አገር እኛን ለማየት መጥተህ በዚሁ አጋጣሚ የአገሩን የጂኦግራፊ አቀማመጥ የተፈጥሮ ውበትና የሕዝቡንም አኗኗር ከፓሲፊክ ውቅያኖስ እስከ አትላንቲክ ከ10,000 ማይል ያካነሰ በመንዝ ያደረግኸውን ጉብኝትና ያሳደረብህን ትዝታ ከአዕምሮህ ሳይጠፋ በትኩሱ በወረቀት ላይ በማስፈር መቻልህ እንደ ትልቅ ነገር የሚገመት ነው። ይህም ምንም እንኳ ከጉብኝትህና ከመዝናናት ጊዜህን ለወደፊቱ ጠቃሚ ማስተወሻና መታሰቢያ ሆኖ እንደምታገኘው አልጠራጠርም።

በራስህ ጥረት ይህ ዕድል አጋጥሞህ ብዙዎቹን የአሜሪካንን ክፍለ አገሮችን ስትጐበኝ እንደተረዳኸው አሜርካኖች በሳይንስና በቴክኖሎጂ በኩል በጣም እተራቀቁ እንደመሄዳቸው መጠንና እርምጃቸውም ከመቼውም ይልቅ እየተፈጠነ ሲሄድ በሌላው ወገን ደግሞ በትልልቆቹ ከተማዎቻቸው ያሉትን የኑሮ ጭንቅንቆችና የሞራል ድክመቶች በሕዝቡም ያለውን የኑሮ አለመመጣጠን አብረህ ለመመልከት በመቻልህ ስለአሜሪካን ያለህ እተሳሰብ ትክክለኛ እንደሆነ እርግጠኛ ነኝ።

ከዚህ በተረፈ ከብዙ ዐመታት በኋላ በጤናና በደስተኛነት ላይህ በመቻሌ ዕድለኛው እኔ ነኝ እላለሁ። በሚቀጥለው ዓመት ደግሞ እማማን እንዲሁ በማየት ዕድል ቢያጋጥመኝ በሕይወቴ ትልቁ ምኞቴ እግቡ ደረሰ ማለት እችል ነበር።

መልካም ጉዞ እየተመኘሁ
ታዛዥ ልጅህ

ፍሥሐ አጥላው

# የአሜሪካን አገር ጉብኝት

**ማውጫ**

ስለአሜሪካን አገር ጉብኝት ያዘጋጀው ማስታወሻ በ28 ገፅ የተፃፈ እንዲሁም ልዩ ልዩ ካርድ ወይም ፎቶግራፎች የሚገኝበት ሲሆን ይኸውም፡-

1. በመግቢያው ላይ የተገለፀው አጭር ማስታወሻ
2. በካሊፎርኒያ ክፍለ ሃገር የተጎበኙት ልዩ ልዩ ሥፍራዎች
   ሀ. በሣንታክላራ፣ ሣን ሆዜና ሳንታ ክሩዝ አካባቢ
   ለ. የኦክላንድ ከተማና የባህር ውስጥ ጉዞ (በባቡር)
   ሐ. ሣን ፍራንሲስኮና በአከባቢው ያሉ ታሪካዊ ድልድዮች
   መ. ሎስ አንጀለስና ዩኒቨርሳል ስቶዲዮ
   ሠ. የሣን ዲዬጎ.ዙ. የአውሬዎች ከተማ
3. የቺካጎ ከተማ
4. ኢንዲያና
5. ኦሃዮ
6. ዋሺንግተን ዲ.ሲ
7. ቨርጂኒያ
8. ኒው ጀርሲ
9. ኒው ዮርክና (የተባበሩት መንግስታት ጽ/ቤት)
10. ተጨማሪ ማስተወሻዎች
   ሀ. ስለሱቆች ለምሳሌ የተጠቀሰ
   ለ. የአሜርካኖች የሣይንስና ቴክኖሎጂ ግስጋሴ
   ሐ. በአሜሪካን ልዩ ልዩ ሶሳይቲ
   መ. ከካሊፎርኒያ ክፍል የኢትዮጵያ ተማሪዎች ኑሮ
   ሠ. በመጨረሻ ጊዜ የታሆ ሃይቅና የኔቫዳ ክፍለ ሃገር ጉብኝት
   ረ. ካልፎሪኒያ ሣንታክለራ በነበርኩበት ጊዜ የነበረኝ የግዜ ማሣለፊያ ፕሮግራም
   ሰ. በመጨረሻም ምሥጋናና ምርቃት

<u>የአሜሪካንን አገር ማየት ለምን ይጠቅማል?</u>

<u>ከአጥላው ወልደ ዮሐንስ የተዘጋጀ የግል ማስታወሻ</u>

# መግቢያ

1. በ1972 ዓ.ም በሚያዝያ ወር አሜሪካን አገር እንድሔድ ተፈቅዶልኝ፤ አንዳንድ የአሜሪካንን ክፍለ ሀገሮችና ከተሞች ለመጎብኘት ስለቻልኩ ከጉብኝቱ ዝርዝር ውስጥ ከኢየሩሳሌም ወደ አቴንስ ተመልሰን በጣም ግዙፍና ምቹ በሆነው በአሜሪካን አውሮፕላን ለመሣፈር ምዝገባው ከተጠናቀቀ በኋላ በመንገደኞች ማረፊያ ሣሎን በመቆየት ስንጠባበቅ፣ በምንጓዝበት አውሮፕላን ውስጥ የሚያገለግሉት ወጣት አሜሪካኖች ወደ ማሣፈሪያው ክፍል ሲገቡ ምንም ብዛታቸው ከ70ና ከ80 የማያንስ ቢሆን ቅልጥፍናቸውና ሁኔታቸው ከነበርንበት አውሮፕላን ከፍ ያለ ልዩነት እንዳለው ይታይ ነበር። ወዲያውኑ እኛም እንደተሣፈርን አስተናጋጆቹ በየሥራ ድርሻቸው በሥርዓት ተመድበው የተሟላ አገልግሎት ለመስጠት ሲንቀሣቀሱና ሲዘጋጁ ይታይ ነበር። አብረን የምንጊዘው ጓደኛዬ ሁኔታው አስገርሞት እነግዲህ ከአሁን ጀምሮ ያለነው አሜሪካን ስለሆነ ከዚሁ አንስቶ ያለውን ለውጥና ልዩነት ልናየው ነው በማለት ገለፀልኝ።

ወዲያው በግል ራዲዮ (ሙዚቃ) ለማዳመጥ ፊልምም ለማየት የሚያስችል ልዩ መሣሪያ መታደል ተጀመረ። የሙዚቃው መስመር 13 ጣቢያ ስላለው እየመረጡ ለማዳመጥ ባለቀለም የሆነውም ፊልም በየአዳራሹ ስላለ እኛም ዘንድ እፊታችን ባለው ሰፊ ሠሌዳ ላይ ተዘጋጅቷል። ሌላው የምግቡ፣ የመጠጡ ዓይነት አቀራረብ የልዩ ልዩ ዕቃዎች ገበያ ሁኔታ ይህን ይመስላል ብሎ ለመግለፅ ቃል አይገኝለትም።

በዚህ ዓይነት ጉዞአችንን ቀጥለን በአትላንቲክ ውቂያኖስ ባህር ላይ ከ11 ሰዓት በረራ በኋላ ኒው ዮርክ ስነደርስ ጓደኛዬ ወዲያውኑ አውሮፕላን ለውጦ ወደ ቺካጐ ጉዞውን ሲቀጥል እኔ ኒው ዮርክ አድሬ በማዕግስቱ ከምሽቱ 12 1/2 ሲሆን ወደ ካሊፎርኒያ በመጓዝ ከኒው ዮርክ ሣን ፍራንሲስኮ 5 1/2 ሰዓት የፈጀውን በረራ ጨርሼ ከሚቀበሉኝ ልጆቼና ሌሎችም ሊቀበሉኝ ከመጡት ኢትዮጵያውያን ተማሪዎች ጋር ተገናኘሁ። ልጆቼ የሚኖሩበት ከሣንፍራንሲስኮ ቀጥሎ በመገኘው ሣንታ ክላራ ወረዳ ሣን ሆዜ የተባለው ከተማ ሲሆን ርቀቱም 50

ማይል ይሆናል። በዚሁ በገባሁበት ዕለት በነበረው ምሽት እኔን ለማየትና እንኳን ደህና ገባህ ለማለት የነበሩት ተማሪዎች በጣም ብዙ ነበሩ። በዚሁ ጊዜ አገራቸውንና ዘመዶቻቸውንም በጠለቀ ናፍቆት የሚያስቡ መሆናቸውን ባነጋገራቸውና ባቀባበላቸው በቀላሉ መረዳት ይቻል ነበር። ይልቁንም ከአዲስ አበባ ያመጣኋቸው ከ15 ያላነሡ ልዩ ልዩ አዳዲስ መጽሔቶች ስለነበሩ እነሱም ያገራችንን የለውጥና የልማት እንቅስቃሴ ወንዙን ደኑንና የዱር አውሬዎችንም ጭምር በሥዕል የሚያሣይ ስለሆኑ ደስታቸው ወሰን አልነበረውም።

አሜሪካን አገር እንደ ደረስኩ የተቀመጥኩት ትልቅ ልጄ ከወንደሙና ከእህቱ ጋር አንድነት ስለሆኑ ከተከራየው አነስተኛ መኖሪያ ቤት ነበር። ይህም አከባቢ ከተማው በሣንታ ክላራ ወረዳ ውስጥ ሣን ሆዜ ይባላል። እንደ እድል ሆኖ ልጆቹ ለመኖሪያ ቤት ያጋጠማቸው ቤት ባለ አንድ ፎቅ ሆኖ ከተሠሩት አፓርታማዎች አንዱ ነው።

የአፓርታማዎቹ ቦታ በኰምፓውንድ ክልል ውስጥ የተወሰነ ግቢውም በጣም ሰፊ ሆኖ በልዩ ልዩ ዛፎች፣ በአትክልቶችና በመስክ ሣሮች የዳበረ፤ በመዘዋወሪያ መንገዶችና መብራቶች ያጌጠ ከመሆኑ በላይ በጋራ የሚጠቀሙበት አልፎ አልፎ ደንበኛ መዋኛ እንዲሁም በፍልውሃ መልክ (እንደጠበል) ለጤንነት የሚያገለግል (ጃኩዚ) ሙቅ ውሃ የሚያፍለቀልቅ አነስተኛ ባህር አለው። ይህም ክብ ሆኖ ዙሪያውን በውሃ ውስጥ እንደ ዳረጃ ያለ መቀመጫ ተደርጎለታል። ጽዳቱና መልኩ ሌላ ነው። በመዋኛው ክፍል ዥንጥላዎች፣ መቀመጫዎችና ጠረጴዛዎች የመዝናኛ አልጋዎች ጭምር በብዛት ይገኛል። ከዚህም በቀር የማረፊያ ሣሎን ከምቹ ወንበሮች ጋር፣ እንደ ከረንቦላና ቢላርድ፣ የጠረጴዛ ኳስ፣ የጅምናስቲክ መለማመጃ መሣሪያዎችም በዚሁ በመዋኛው አጠገብ ይገኛሉ። ከዚህም በቀር ለተከራዮቹ ብቻ የሚያገለግል አማካይ በሆነ ስፍራ በግቢው ውስጥ የልብስ ማጠቢያ ላውንድሪ ይገኛል።

አፓርታማው የግል ኩባንያ ሲሆን በግቢው ውስጥ ከተከራዩት ሰዎችና የነሱ እንግዶች ከሆኑት በቀር ሌላ ለመጠቀም አይችልም በአፓርታማው የተከለለው ቦታ በጠቅላላው ጽዳቱም ሆነ አትክልቶቹ፣ የመዋኛውና የመዝናኛው አካባቢ ሁሉ የሚጠበቀው በአፓርታማው

ኩባንያ ስለሆነ በሰፍራው ላይ አንዳችም ጉድለት አይታይም። ሥራው በአንዲት አሜሪካዊት ሴት ማናጀር የሚካሄድ ሲሆን ጽህፈት ቤቱም እዚህ በአንደኛው አካባቢ ይገኛል።

ከዚህ ቀጥሎ ወደ ጉብኝቱ ዝርዝር በመግባት አንዳንድ መግለጫዎች ፅፌአለሁ።

2. ካሊፎርኒያ (CALIFORNIA)

ሀ/ ካልፎርኒያ የተባለው ክፍለ ሀገር ትልቅና ሰፊ ከተባሉት የአሜርካን ስቴቶች አንደኛው ነው። በዚሁ ክፍለ ሀገር ውስጥ በሣንፍራንሲስኮ አቅራቢያ የሚገኘውን በሣንታ ክላራ ወረዳ የሣን ሆዜንና የሣንታ ክሩዝን አካባቢ አገለገለሁ።

በአሜርካን አገር ካሉት አገሮች ለመኖሪያም ሆነ ለሥራ በአቀማመጡም ባየሩ በጋራው፣ በተፈጥሮ ደኑ ስመጥሩ የሆነው ባንድ ፊት የፓስፊክ ውቂያኖስ ባንድ ፊት ደግሞ በጋራና በደን የተከበበው ሣን ሆዜ የተባለው ለጥ ባለ ሜዳ ላይ የተሠራው ከተማ እንደ ሌሎቹ ከተሞች ሰማይ ጠቀስ ፎቆች ብዙ አይኖርበትም ፎቅና ቪላዎች ናቸው። ከሣን ሆዜ ከተማ አቅራቢያ የሚገኘው ሣንታ ክሩዝ የተባለው ደግሞ የፓስፊክ ውቅያኖስን ድንበር ይዞ የሚገኝ ሲሆን በዚሁ ከተማ ወደ ባህሩ ያለው ቢች ብሮድ ዎክ ተብሎ የሚጠራው ለሕዝብ መናፈሻ፣ መዝናኛና መደሰቻ በልዩ ልዩ የሕዝብ አገልግሎት ድርጅቶች ያጌጠ ነው። ቤቶቹ የተሠሩት በባህሩ ላይ ጭምር ስለሆነ አገር ጐብኝዎች የሚጐርፉበት በመሆኑ በየሱቆቹ የሚታዩት ዕቃዎች ዓይነት ለጐብኝዎች እጅግ የሚያስደስቱና ታይተው የማይጠገቡ ናቸው ። በተለይም ልዩ ልዩ የሆኑትን የመዝናኛ ክፍል ለማየት ቢፈለግ ባንድ ቀን ለማዳረስ ያዳግታል። ለምሳሌ ያህል እንጂ በሙሉ ቀርቶ በከፊልም ለማሣየት ያስቸግራል። የመጫወቻው ዓይነትና ብዛቱ ከ500 አያንስም።

ከሣን ሆዜ ከተማ ወደዚሁ ስፍራ የሚወሰደው በደኑ ውስጥ ጋራውን አቋርጦ ስለሆነ ሁለት ፍሪዌይ መንታ መንገዶችና ፍሪዌይ ያልሆኑ ደግሞ በየአቅጣጫው ይገኛሉ። በበዓል ቀን ወደዚር መዝናኛ ሥፍራ የሚሄደው የመኪና ብዛት ባነስተኛ ግምት ከ150 ሺህ አያንስም።

በሳን ሆዜ አካባቢው ባለው ጋራ የሚገኘው የተፈጥሮ ደን እከተማው ውስጥ ሆኖ ሲታይ በጣም የሚያስደስት አቀማመጥ አለው። ወደ ደኑ ለመግባት በየአቅጣጫው ደኑንና ጋራውን የሚያቋርጡ አስፋልት መንገዶች ተሠርተዋል። ደኑን ለማቋረጥ ከ100 ማይልስ ያካነሰ መጓዝ ያስፈልጋል። በየሥፍራው አልፎ አልፎ ፏፏቴ የህዝብ መናፈሻዎች ይገኛሉ።

ለ/ ሣንፍራንሲስኮ (SAN FRANSISCO)

የሣንፍራንሲስኮ ከተማ ታሪካዊ ስም ያለው ነው። ከዚህም አንዱ እ.ኤ.አ በ1945 ዓ.ም የተባበሩት መንግስታት ቻርተር የተፈረመበት ነው። ከተማው በአብዛኛው ክፍል የፓስፊክ ውቅያኖስ በወሽመጥ ገብቶ የሚያዋስነው ሲሆን ከተማው ጋራ ላይ የተመሠረተ ነው። ዘመናዊ የሆኑ ሰማይ ጠቀስ ፎቆችም በብዛት ይገኙበታል። በከተማው ውስጥ የሚተላለፉት መንገዶች እንደ ድልድይ ሆነው ከላይና ከታች መኪና ሲጐርፍ የሚታይባቸው ሲሆን ከተማው በህንፃ ብዛት የተጣበበ መስሎ ይታያል። ከዚሁ ከተማ ቀጥሎ አንዱ ወደ ኦክላንድ ከተማ ባህሩን አቋርጦ የሚሔድ ታላቅ ድልድይ ቤይብሪጅ አለ። ይህም ፍሪዌይ ነፃ የመብረሪያ መነገድ ከላይና ከታች እንደ ፎቅ ሆኖ ለመሔጃና መመላሻ የተሠራ ነው ። እንዲሁም ከሣንፍራንሲስኮ ከተማ ባንድ ክፍል ወደ ሰሜን ካሊፎርኒያ የሚያሻግር ታሪካዊ የሆነ ድልድይ ባህሩ ላይ ተሠርቷል። ጐልደንጌት በዓለም ውስጥ ተወዳዳሪ የሌለው ለመሆኑ ጽሑፍ ያስረዳል ።

ሐ/ ኦክላንድ (OAKLAND) ኦክላንድ የሚባለው ከተማ ከሣን ሆዜ በቅርበቱም ሆነ በትልቅነቱ ከሣንፍራነረሲኮ ቀጥሎ የሚገኝ ነው። የኦክላንድ ከተማ በጣም ደማቅና ትላልቅ ፎቆች የሚገኝበት ሲሆን ጥቁሮች የሚበዙበት ልዩ ልዩ ፋብሪካዎች ያሉበት ስለሆነ ኢትዮጵያውያኖችም በብዛት ይገኙበታል። ኦክላንድ ከሣንታ ክላራ እሩቅ ባለመሆኑ እዚያ የሚገኙ ኢትዮጵያውያን ተማሪዎች ግብዣ እያደረጉልኝ በየጊዜው ተመካልሼ ተመልክቼዋለሁ። በኦክላንድ ከተማ መካከል ስመጥሩና በካሊፎርኒያ ውስጥ በጣም የታወቀው በርክሊ የተባለው ዩኒቨርሲቲ ይገኛል። (UNIVERSITY OF BERKLEY) ከዚህ ዩንቨርስቲ ተመርቀው የሚወጡት ከፍተኛ

ግምት የሚሰጣቸው ናቸው። በዩኒቨርሲቲው እስከ 35 ሺ ተማሪዎቸ ይገኛሉ። ዩኒቨርሲቲው የሊበራል እንቅስቃሴ የሚታዩበት ስለሆነ ማናቸውም የንግግር ነፃነት የሚካሄድበት ነው። በዚሁ ከተማ የሚኖሩ ጥቁር አሜሪካኖች በዝቅተኛ የኑሮ ደረጃ የሚገኙ ስለሆነ የጥቁሮች ሠፈር የሆነው ቀበሌ ከሌላው ክፍል ደከም ብሎ ይታያል። ቢሆንም የኦክላንድ ከተማ በአየሩ ጠባይና በአቀማመጡም ዳገትና ሜዳ፣ ጋራና ሸንተረር ስላለበት ከዛፎቹ ድምቀት ጋር በጣም የሚያምርና የደስ ደስ ያለው ነው።

ከሣንፍራንሲስኮ ከተማ ወደ ኦክላንድ ከሚያስኬደው ታሪካዊ ከሆነው ድልድይ ሌላ ከባህር በታች በመሬት ውስጥ ደግሞ ፈጣን የሆነ የባቡር መስመር አለ። ይህም ከሣንፍራንሲስኮ ይነሣና ባህሩን አቋርጦ በኦክላንድ ከተማ መካከል የሚሄድ አገር አቋራጭ ባቡር ነው። በባቡር በሔድንበት ጊዜ ከምድር ውስጥ ገብተን ባለው የባቡር ጣቢያ ከመሣፈር ተሰልፎ የሚገኘውን ህዝብ ብዛት አይተን እኛም በተራችን በመሰለፍ ስንመለከት የመሣፈሪያውን ትኬት ቆርጦ የሚሰጠው የኰምፒውተር መሣሪያ መሆኑን ተረዳን። መጀመሪያ ምንዛሪ ያስፈልግ እንደሆን ቅንስናሽ ገንዘብና ሌላውንም ለመመንዘር የተዘጋጀ ማሽን አለ። የምንዛሪው ገንዘብ ከተዘጋጀ በኋላ ወደ ትኬት ክፍል ቀርቦ ለምትሔድበት ጣቢያ በሰሌዳው ላይ የተለጠፈውን የዋጋ ዝርዝር አይቶ በማሽኑ ውስጥ ይከተትና ወዲያውኑ የመሣፈርያው ካርድ ከተፍ ይላል። ካርዱን ተቀብሎ ወደ መሣፈሪያው ክፍል ሲገባ ካርዱን ባንድ ማሽን ውስጥ በማስገባት መተላለፍያው ይከፈትና ካርዱ ለተሣፋሪው ወዲያውኑ በሌላ ቀዳዳ ይመለስለታል። ከሚወርድበት ጣቢያ ሲደርስ ባቡሩ ስለሚቆም የተሣፈረበትን ካርድ በአንድ ማሽን ውስጥ ሲከተው መተላለፊያው ይከፈታል። የተሣፈረበትን ካርድ ሣያስገባ ማንም ሰው መተላለፍ አይችልም። ምናልባት በምንዛሪ ምክንያት የቀረ ገንዘብ ቢኖር በሩ በሚከፈትበት ጊዜ ተመላሹን ገንዘብ ከማሽኑ ይቀበላል። ራሱም በተሣፈረበት ጊዜ የጐደለበት ሒሣብ ቢኖር ልዩነቱን ለማሽኑ ካልከፈለ ካርዱንም ቢመልስ በሩ አይከፈትለትም። ይህ ሁሉ ሲሆን ኰምፒውተሩ ብቻውን እንጂ አንድም ሠራተኛ የለም ።

መ/ ሎስ አንጀለስ (LOS ANGELES)

ሎስ አንጀለስ የካሊፎርኒያ ጠቅላይ ግዛት ትልቁ ዋና ከተማ ሲሆን ለአሜሪካን አገር 3ኛ ከተማ ነው። ሎስ አንጀለስ ከሳንፍራንሲስኮ ወይም ለሣንታ ክላራና ሣን ሆዜ 450 ማይልስ ርቀ የሚገኝ መንገዱ በልዩ ልዩ አቅጣጫ የተዘረጋ ስለሆነ ወደ ሎስ አንጀለስ የሔድነው በአውቶሞቢል ነበር። አንደኛው የመኪና መንገድ የፓስፊክ ውቂያኖስን ባህር ዳርቻ ሣይለቅ ባህሩን እየተዋሰነ የሚዘልቅ ነው። በጉዞው ላይ አልፎ አልፎ በሚገኙ መዝናኛ ሥፍራዎች እያረፍን ሎስ አንጀለስ ከተማ ገባን ። በዚሁ ዕለት ያመሸነው ካሊበካ በተባለው የኢትዮጵያውያን ምግብ ቤት በመሆኑ ብዙ ኢትዮጵያውያኖች ለማግኘት ችለናል። እንዲሁም በዚሁ ምሽት ሆሊ ውድ የተባለውን አካባቢ እየተዘዋወርን ተመልክተናል።

በማግስቱ ከጠዋቱ 2 ½ ሰዓት ተነስተን ከሎስ አንጀለስ ከተማ 25 ማይልስ ርቀ ከከተማው ተያይዞ የሚገኘውን ዝናው በዓለም የታወቀውንና ተወዳዳሪም የሌለውን ዩኒቨርሳል ስቱዲዮን (UNIVERSAL STUDIO) ለመጐብኘት በአውቶሞቢል ሔድን። የስቱዲዮው አብዛኛው ክፍል አጋራ ላይ የተመሠረተ ሲሆን አካባቢውም ዳገትና ሜዳ፣ ወንዝና ሸንተረር፣ ደንና ጫካ ፣ ባህርና ፏፏቴ፣ የባቡር ጣቢያና ኤርፖርትም ሣይቀር የሚገኝበት ደንበኛ ከተማ ነው። ከጣቢያው ስንደርስ ከኛ ቀድመው የሚገኙ ብዙ ቱሪስቶች ተሰልፈው ትኬት ለማግኘት ተራቸውን ሲጠብቁ አገኘን። እኛም ወደ ሰልፍ ስፍራ ባንደኛው መስመር ተጠግተን ካንድ ሰው ሰባት ብር ተኩል የሚከፈልበትን የመግቢያ ካርድ ካገኘን በኋላ ለጐብኝዎች በተዘጋጀው እንደ ባቡር ፉርጐ በተቀጣጠለው አውቶቡስ ተሣፍረን ወደ ፊልም መቅረጫው ከተማ በመግባት ጉዞአችንን ቀጠልን። ከአስጐብኚዎቹ ያለማቋረጥ የሚሰጠው መግለጫ ሣይዛነፍ የፊልም አሠራሩን ሁኔታና አክተሮቹን ለማየት የሚተክተውን የፊልም መቅረጫ ተንቀሣቃሽ መሣሪያ በየደረጃው እያሣዩን ጉዞአችንን በአቶቡስ በመቀጠል ፊልም ቀራጮችም ኢክስፖርቶች በየክፍሎና በየሥራ ድርሻቸው ሲንቀሣቀሱ ይታዩ ነበር። ትርኢቱን በመመልከት ጉዞአችንን ቀጥለን ልዩ ልዩ ቀላል ምግብም ሆነ መጠጥ በመውሰድ ጉብኝቱ ከጧቱ 3 ½ ሰዓት ጀምሮ ሣይቋረጥ ወደት አቅጣጫ

እንደተጓዝንም ሳይታወቀን ልክ ጠዋት አውቶቡስ ከተሳፈርንበት ጣቢያ ስንደርስ ጊዜው አስር ሰዓት ስለሆነ የዛሬው የጉብኝት ፕሮግራም የተፈፀመ መሆኑን ስለገለፁልን ወደ የመጣንበት ተመለስን።

እዚህ ላይ ለመግለጥ የምወደው ይህ እየተዘዋወርን የጐበኘነው ከተማ በሲኒማ የምንመለከተው ፊልም እንዴት እንደሚሠራ እውነተኛውን ግልጥ አድርጐ የሚያሣይ የማያጠራጥር ትክክለኛ ማስረጃ መሆኑን ነው። ማንም ሰው የሲኒማ ማየት ልማድ ኖሮት ለረጅም ጊዜ ሲመለከት ኖሮ ይህን የፊልም መቅረጫ ዩኒቨርሳል እስቱዲዮም በጐበኘ ጊዜ ለፊልም የከፈለው ገንዘብ እውነትነት ለሌለው ነገር መሆኑን ይረዳል። ደግሞም በሌላ አስተሳሰብ፣ ይህን ታሪካዊ የፊልም መቅረጫ እስቱዲዮም የተመለከተ ሁሉ የሲኒማ ፊልም ፈፅም ውሸት መሆኑን ሲረዱ ባለሲኒማዎችን ኪሣራ ያመጣባቸዋል ተብሎ የሚወሰድ ግምት ሳይኖር ምስጢሩን ግልፅ አድርገው ማሣየታቸው የሚያስገርም ነው።

ሠ/ ሣን ዲዬጐ (SAN DIEGO)

በማዕግስቱ ከጠዋቱ ሁለት ሰዓት ተነስተን ከሎስ አንጀለስ ከተማ 100 ማይልስ እርቆ የሚገኘውን፣ በዓለም ተወዳዳሪ የለውም የሚባለውን ሣን ዲዬጐ የሚገኘውን ታሪካዊ የሆነውን ዙ የልዩ ልዩ አውሬዎች ከተማ ለመጐብኘት ጉዞአችንን በመኪና ቀጠልን። ከሎስ አንጀለስ ወደ ሣን ዲዬጐ በሚወስደው መንገድ እየተመለከትን ያለፍነው አገር በእርሻና በአትክልት በደን የዳበረ ሆኖ ይታያል። ሣን ዲዬጐ ስንደርስ አውሬዎች ከሚገኙበት ቀበሌ ከመድረሣችን በፊት ትኬት ከሚሸጥበት የተለየ ራቅ ያለ ቦታ ተሰልፈን የመግቢያውን ካርድ ካገኘን በኋላ በፊልም መቅረጫው እስቱዲዮም እንደተደረገው ለዚሁ ስፍራ የሚያገለግሉ እንደባቡር ተቀጣጥለው በተሠሩ አውቶቡሶች ውስጥ በሆነውና ወደ አውሬዎቹ ከተማ ጉዞ ቀጠልን። ፍፁም የተፈጥሮ ደን በሆነው በረሃ ወይም ገጠር በሚመስል አካባቢ ስንደርስ አውሬዎቹ በያይነታቸው ክፍል ክፍል ተደርጐላቸው እየተንጐራደዱ ከአንዱ ወደ አንዱ ክፍል መተላለፍና መተያየት እንዳይችሉ ሆኖ በተሰራ የተፈጥሮ ገደል ዓይነት ተከልሎላቸዋል። ባህር፣ ፏፏቴ፣ ዛፍ ወይም ገደል ወይም አቧራማ ቀበሌ ሣርና ቁጥቋጦ ሳይቀር በተፈጥሮ ጠባያቸው በሚያምር ሁኔታ የተዘጋጀላቸውን የየራሣቸውን ክፍል ዙሪያውን

ክፍት በሆነው አውቶቡስ ውስጥ እንዳለን እየተዘዋወርን ተመለከትን። እዚያው ተወልደው እስኪያረጁ ድረስ የሚቀመጡበት ወይም የሚንቀሣቀሱበት ስፍራ ከፍላጐታቸው ምንም ጉድለት የሌለው ከመሆኑም በላይ ፅዳቱ ሰው እንደሚቀመጥበት የተጠበቀ ነው። ይህ የዓውሬዎች ከተማ በዓለም ላይ ተወዳዳሪ የሌለው መሆኑንም ከአጐብኝዎቹ ከመገለጡም በላይ ልዩ ልዩ ፅሁፍ በየሥራውና በየጣቢያው ከአውሬዎቹ ሥዕል ጋር ተዘጋጅቶ ይገኛል። ሌላው ቀርቶ የዘንዶውና የእባቡ ዓይነት ከሣምሣ በላይ እንጂ አያንስም። ጉብኝቱ ቀኑን ሙሉ የፈጀ ስለሆነ በተሣፈርንበት አውቶቡስና አንዳንድ ጊዜ በእግራችን ወርደን በማየት ስንዞር ውለን በመጨረሻም በአየር ላይ በሚንሳፈፍ ተሽከርካሪ እየተሣፈርን የቀበሌውን አቀማመጥ በማየት ተጉዘን ጧት አውቶቡስ ከተሣፈርንበት ጣቢያ ስለደረስን የጉብኝቱ ፍፃሜ መሆኑን ገለፁልን። በዚሁ ቀን ወደ ማታ ከጉብኝቱ ስንመለስ በሣን ዲዬጐ ከተማ የሚገኘውን ፓርክ የተባለ እጅግ ያማረና ደስ የሚያሰኝ መናፈሻ ተመለከትን። በሚያማምሩ ህንፃዎችና ፏፏቴዎች መካከል አልፎ አልፎ ሆቴሎች ስላሉ እኛም በአንዱ ሆቴል ገብተን ደስ የሚያሰኝ መስተንግዶ ከተደረገልን በኋላ ወደ ሎስ አንጀለስ የመልስ ጉዞ አደረግን። ይህ ሣን ዲዬጐ የተባለው ከተማ በአሜሪካ አገር ወይም ከሌላ አገርም ቢሆን በእድሜ ባረጁ ጊዜ በጡረታ ላይ ያሉ አንዳንድ ሃብታሞች በመጨረሻ ዘመናቸው ወደዚህ ስፍራ በመምጣት በአየሩ መልካምነትና በቦታውም ውበት ደስ ብኳቸው የሚኖሩበት መሆኑን አስረድተውናል። ከሎስ አንጀለስ ስንመለስ በእርሻ ለም የሆነውንና ቤንዚን በየቦታው የሚወጣበትን እየተመለከትን በሌላ መንገድ ስለመጣን ጉዞአችን በጣም ያስደስት ነበር።

ካሊፎርኒያ ከሌሎች እስቴቶች የሚለይበትና ኑሮ የሚፈለግበት ልዩ ልዩ ምክንያቶች አሉት። ይኸውም በአየሩ ጣባይ ሙቀት ወይም ቅዝቃዜ ስለማያጠቃው ጋራ፣ ሸንተረር፣ ፈሳሽ ወንዝ፣ ፏፏቴ፣ የተፈጥሮ ደንና ጫካ ስላለበትና በረዶ አውሎ ንፋስ ስለሌለ እንዲሁም የፓስፊክ ውቂያኖስ ባህር አብዛኛውን ወሰን ስለሚነካው በወሽመጥ እየገባ ብዙ ስፍራ ላይ ስለሚገኝ ከዚህም በቀር የፊልም መቅረጫው

አስቱዲዮና በዓለም ተወዳዳሪ ያለውም የሚባለው ዙ የአውሬዎች ከተማ በዚሁ ክፍል ስለሚገኝ ነው።

በካሊፎርኒያ ጠቅላይ ግዛት ከሚገኙት አገሮች ከዚህ በላይ እንደተገለፀው አንዳንዶቹን ከጐበኘሁ በኋላ ኒው ዮርክ የተለያየነው ጓደኛዬ ከችካጐ ወደ ካሊፎርኒያ የሚመጣ መሆኑን ነግሮኝ ስለነበረ በሚመጣበት ቀን ከሣንፍራንሲስኮ ኢንተርናሽናል ኤርፖርት ሔደን ከተቀበልነው በኋላ ሣን ሆዜ አብረን ስለቆየን የሣን ፍራንሲስኮ አካባቢንና የኦክላንድን ከተማ ታሪካዊ የሆኑትን የባህር ላይ ድልድዮችና የባህር ውስጥ የባቡር ጉዞ እንዲሁም በፓስፊክ ውቂያኖስ አካባቢ የሚገኘውን የሣንታ ክሩዝን ከተማ በሣንታ ክላራና ሣን ሆዜ አካባቢ ባለው ጋራ ላይ ደምቆ የሚታየውን የተፈጥሮ ደንና ሸለቆዎች አብረን ስንጐበኝ ሰንብተን ሌሎችን አንዳንድ አገሮች ደግሞ ለማየት በአሜሪካ አየር መንገድ አውሮፕላን ወደ ችካጐ ጉዞአችንን ቀጠልን። የተሣፈርንበት አውሮፕላን ወደ ቺካጐ ጉዞአችንን ስንጀምር እዚያ የሚገኘው የጓደኛዬ ልጅ ከትምህርት ቤት ጓደኞቹ ጋር ተቀበሉን።

3/ ችካጐ

የችካጐ ከተማ በሰማይ ጠቀስ ፎቆች በዓለም ተወዳዳሪ የሌለው ከመሆኑም በላይ ብዙ ፋብሪካዎችና ኢንዱስትሪዎ የሚገኙበት ከአሜሪካን ሁለተኛ ከተማ ነው። በችካጐ ከተማ እንደ ኤውሮፓ አቆጣጠር በ1970 ዓ.ም በተቆጠረው መሠረት 3,369,000 ህዝብ የሚኖርበት ከመሆኑም በላይ ከከተማው ጋር ተያይዞ የሚገኘው ባህር (ሌክ ሚሺጋን) ባንዳንድ አቅጣጫ ወደ ከተማው ስለሚገባ ብዙ ቤቶችና መንገዶች የተሠሩት በባህሩ ላይ ነው። በዚሁ ባህር ላይ የመርከቦችም መተላለፊያ በመሆኑ መርከቦቹ በሚተላለፉበት ጊዜ በባህሩ ላይ የተሠሩት ሰፋፊ የመኪና መንገዶች በኤሌትሪክ ሃይል አውቀው ይከፈቱና መርከቦች ካለፉ በኋላ ተመልሰው እንደነበር ይሆናሉ። ሌላው ቀርቶ ለመኪና መቆሚያ ፓርኪንግ ከሕንፃዎቹ 15 ፎቅ ድረስ ያለው ሲመደብ ከዚያ በላይ ሃምሣና ስልሣ የሚሆነው ፎቅ ደግሞ መኖርያ ቤትና ቢሮ ነው። መኪናዎቹ እስከ 15ኛው ፎቅ ድረስ ባለው ማቆሚያ በቁጥር በተመደበላቸው ማቆሚያ ከመጠቀም ወደፎቅ ሲያሽከረክሩ እንደዚግዛግ ሆኖ በተሠራው ዳገት ሊወጡና

ሊወርዱ ያለችግር ሲበሩበት ይታያል። ከዚህ ጋር እንደተመለከተው ሰማይ ጠቀስ ህንፃ ከሆኑት ባንደኛው በ96ኛው ፎቅ ላይ አንድ ቀን ምሽት ተጋብዘን በሊፍቱ ስንወጣ ከፍጥነቱ የተነሣ ጭው ብሎ ጆሮ ይደፍናል። 95ኛው ፎቅ ታላቅ ምግብ ቤት ሲሆን 96ኛው ደግሞ ኦርኬስትራ የሚጫወትበት ሆኖ የመጠጥና የመዝናኛ ክፍል ነው።

በምግብ ቤቱም ሆነ በመጠጡ ክፍል ሆኖ የችካጐን ከተማ አንድ ሳይቀር ወለል አድርጐ ያሳያል። በተለይ ማታ በመብራት አሸብርቆ ሲታይ ያለው ውበት ድምቀት የመንገዶች መስመር ቁልፍ ብለው ሲታይ ሁኔታውን ለመግለፅ ቃል ሊገኝለት አይችልም። የችካጐ ከተማ ምንም መንገዱ ሰፋፊ ቢሆን የትራፊክ ጭንቅንቅ ስለሚበዛ አብዛኛውን ህዝብ ወደየተግባሩ የሚመላለሰው በምድር ውስጥ ባቡር ነው። ችካጐ በየስፍራውና በተለይም የባህሩን መስመር ይዞ ብዙ የመዝናኛ ስፍራዎች ይገኙበታል። ዳውን ታውን የሚባለውን ታሪካዊ ከተማነቱን ሊያረጋግጥ ይችላል። ችካጐ ከካሊፎርንያ ክፍለ ሃገር በሰዓት አቆጣጠር የሁለት ሰዓት ልዩነት አለው።

4/ ኢንዲያና

ኢንዲያና የተባለው ክፍለ ሀገር በኢንዱስትሪና በእርሻ የበለፀገ ሲሆን ከተማው እነደችካጐ በትልቅነት የማይጠራ መለስተኛ ከተማ ነው። በከተማውም ብዙ የተፈጥሮ ደንና ዛፍ የሚገኝበት ከመሆኑም በላይ አብዛኛው ቤቶች እንደ ቪላ ሆነው የተሠሩ ናቸው። ከተማውን የሚያቋርጥም ታላቅ ወንዝ ይገኛል። ኢንዲያና የገበሬዎች አገር ስለሆነ ከጉብኝታችን አድናቆትን የሰጠነው የርሻዎቹና የገበሬዎቹ መንደር ሁኔታ ነው።

5/ ኦሃዮ

ከኢንዲያና ጉብኝት በኋላ የተጌዝነው ወደ ኦሃዮ ክፍለ ሀገር ነው። ኦሃዮ በሰዓት አቆጣጠር ከኢንዲያናና ከችካጐ ጋር ያንድ ሰዓት ልዩነት ሲኖረው ከካሊፎርኒያ ጋር ደግሞ የ3 ሰዓት ልዩነት አለው። ኦሃዮ ከኢንዲያና ወሰን ጀምሮ በርሻና በከብት ርቢ ሥራ ከፍተኛ ዝና ያለው መሆኑ ስለሚነገር በእርግጥም እንደተባለው አገሩ በሙሉ በእርሻና በደን የበለፀገ ነው። ከዚህም በቀር በየቦታው ፋብሪካዎች

አሉ። ባየናቸው ከተሞችም የረጂም ዘመን ታሪክ ያላቸው ልዩ ልዩ ኰሌጆች በብዛት ይገኛሉ። ከነዚሁ ውስጥ ኢበርሊንና ዲያፋንስ የተባሉትን ጐብኝተናቸዋል። በኦሃዮ ክፍለ ሃገር ከተመለከትናቸውም አንዱ የጄኔራል ሞቶርስ (የአውቶሞቢል ፋብሪካ) ሲሆን ይህንን ፋብሪካ ለመጎብኘት ፕሮግራም ተደርጐልን ከከተማው ውጪ ርቆ በሚገኘው በዚሁ ፋብሪካ ስንደርስ እንደኛው ለመጐብኘት የተቀጠሩ ብዙ ሰዎች ባዳራሹ ውስጥ አገኘን። ከዚያም በተሰጡን አስጐብኝዎች አማካይነት እንደ ባቡር ፉርጐ ተቀጣጥሎ በሚጌዝ ክፍት ተሽከርካሪ ሆነን የሚሠራው መኪና ልክ እንደ ልሙጥ ቆርቆሮ ሆኖ ከሚገኝበት ከወለሉ ተነስቶ ማናቸውም ጣጣ አልቆለት ወደሚሸጥበት የገበያ አዳራሽ እየተነዳ እስኪገባ ድረስ ሥራውን አንድ በአንድ እያከታተልን አይተናል። አብዛኛው ሥራ የሚከናወነው በኰምፒውተር መሣሪያ ስለሆነ አልፎ አልፎ አስፈላጊ ከሆኑ ሥራዎች በስተቀር የሰው ሃይልና ጉልበት አይጨመርበትም። ፋብሪካው በየሁለት ደቂቃ 3 መኪና የሚያወጣ ሲሆን በመጨረሻው እርከክብ ላይ ዋጋው ጭምር ተፅፎ ያልፋል። በጉብኝቱ ወቅት በፋብሪካው ውስጥ አንድ ኢትዮጵያዊ ስላገኘን በበለጠ ዝርዝር ሁኔታዎቹን ሁሉ አስረድቶናል። የሱም የሥራ መደብ በሒሣብ ክፍል ሆኖ በፋብርካው ውስጥ በጊዜያዊነት ለሚሠሩ የቀን ሙያተኞች አበል ብቻ በአንድ ሣምንት 25 ሚሊዮን ብር ስለሚከፈላቸው፣ የነሱ ሒሣብ በሚዘጋጅበት ክፍል የሚሠራ መሆኑን ገልፆልናል። በኢንዲያና፣ በኦሃዮ ጉብኝታችን ጊዜ የገበሬዎቹን መንደር ወይም ቀበሌ ስመለከት በእርሻውና በከብት እርባታው ጣቢያ አንድ ሠራተኛ አይታይም። አልፎ አልፎ ቢታይ ገበሬው ከሚስቱና ከልጆቹ ጋር ሆኖ በየቤታቸው አካባቢ ሲዝናኑ ነው። ከሥራውም የሚሠማሩት ራሱ ገበሬውና ሚስቱ ናቸው እንጂ ተጨማሪ ሠራተኛ የሌላቸው መሆኑንና ገበሬውም ወይም ሚስቱና ልጆቹ ትራክተሩን ይዘው በሚያርሡበት ጊዜ በትራክተሩ ላይ ከነጅው በልዩ ሆኖ በተሠራው ባለመስተዋት መቀመጫ ውስጥ ሙዚቃና ራዲዮ እያዳመጡ ድካም ሣይሰማው ማናቸውንም የርሻና የሰብል ስብሰባ ተግባር የሚያካሂድ መሆኑን ገልጦልናል።

በኢንዲያናና በኦሃዮ ያደረግነውን የአንድ ሣምንት ጉብኝት እንደፈፀምን ወደ ችካጐ ተመለስን። ጥቂት ቀናት ውለን ካደርን በኋላ በዚያ ክፍል ያለውን ጉብኝት በማጠናቀቅ የጓደኛዬ ልጅ በጣም ደስ የሚያሰኝ የአቀባበልና የጉብኝት መስተንግዶ ካደረገልን በኋላ ጉዞአችንን ወደ ዋሽንግተን ዲሲ ቀጠልን።

ከቺካጐ ወደ ዋሽንግተን ዲሲ የሔድነው በጣም ፈጣንና ምቹ በሆነ ባቡር በመሆኑ ሁለት ቀን ሙሉ የፈጀውን መንገዳችንን ምቾቱን ሳንጠግበው ዋሽንግተን ዲሲ ገባን። በውነት የባቡሩን ምቹነት ለመግለጥ ምንም በቂ ቃል ባይገኝለት ባጭሩ ለመጥቀስ ያህል፡- ችካጐ ያለው የምድር ውስጥ ባቡር ጣቢያ ራሱ እንደትልቅ የገበያ አዳራሽ ከመሆኑም በላይ ማናቸውም ሱቅም ሆነ የመንገደኞች እንቅስቃሴ በሥርዓት ይካሔዳል እንጂ ትርምስምስና ጫጫታ የሚባል ነገር የለም። እኛም ቀደም ባለው ቀን ለጉዞው ተመዝግበን ስለነበር እንድንገኝ የተነገርንን ሰዓት አክብረን ከመሳፈሪያው ሥፍራ ተራችንን ጠብቀን በመሰለፍ ከቀረብን በኋላ አስፈላጊውን ክፍለን የማለፊያ ካርድ በመቀበል ጉዞአችንን ቀጠልን። የባቡሩ ጣቢያ ከመሬት ውስጥ ይሁን እንጂ ከጣቢያው ሲወጣ በመሬት ላይ የሚጓዝ ነው። ወንበሩ ልክ እንደ አውሮፕላን መቀመጫ ሆኖ በቀላሉ ለመዘርጋትና ለመተኛት የሚመች፣ ለእያንዳንዱ የግል መብራትና ኤር ኰንዲሽን ያለው ሲሆን በየአቅራቢያው ወረፋ የሌለው መታጠቢያ ቤት አለ። ውስጥ ለውስጥ ባለው መተላለፊያ በመጓዝ ወደ ምግብ ቤቱ ምቾት፣ ያስተናጋጆቹ ቅልጥፍና እውጪ በየሆቴሎቹ ወይም አውሮፕላን ላይ ከሚደረገው መስተንግዶ ከፍ ያለ ብልጫ አለው። በምግብ ማዘጋጃው ክፍል የሚፈለገው ከታዘዘ በኋላ ምግቡንም ሆነ መጠጡን ተቀብሎ ቢፈልግ ከምግብ ቤቱ ጠረጴዛ ላይ ካልፈለገም ከመቀመጫው ወንበር ጋር ተያይዞ በሚገኘው ጠረጴዛ ላይ ሔዶ ሊጠቀም ይችላል። ከዚህም በቀር የተለየ መኝታ ለሚፈልጉ ፍፁም ምቾት ያለው ክፍል ስላለ ሒሣቡን ከፍሎ አልጋ ላይ ሊተኛ ይችላል። በዚህ ዓይነት ምንም ሳይታወቀን 24 ሰዓት ከተጓዝን በኋላ ዋሽንግተን ዲሲ ደረስን። የዋሽንግተን ባቡር ጣቢያ ምንም በሞደርንነቱ ብልጫ ቢኖረው ሌላው እንደ ችካጐ ተመሳሳይ ስለሆነ አዲስ ነገር መስሎ አልታየንም።

## 6/ ዋሽንግተን ዲሲ (WASHINGTON DC)

ዋሺንግተንዲሲእንደደረስንከማረፊያየተያዙልንፔንሲዮንበኢትዮጵያ ኤምባሲ አጠገብ ስለነበረ ከማረፊያችን ዕቃችንን አስቀምጠን ወዲያውኑ ወደ ኤምባሲያችን በመሄድ ኃላፊዎቹን ተዋወቅናቸው። እነሱም መልካም አቀባበል በማድረግ በጽሕፈት ቤታቸው ካነጋገሩን በኋላ የሚያስፈልገንን ጉዳይ ቢኖር በሚቻላቸው ሁሉ የሚረዱን መሆኑን ገልፀውልን ወደ ማረፊያችን ተመለስን። የዋሽንግተን ከተማ እንደምነገምተው ከሌሎቹም ታላላቅ ከተሞች በምኑም በምኑም ብልጫ ያለው ይመስለን ነበር። ነገር ግን የዋሽንግተን ዲሲ በጣም ትንሽ ከተማ ከመሆኑም በላይ የዋይትሃውስ ቤተ መንግሥትም ላንድ ሰው መኖሪያ እንደተሰራ ቪላ ቤት ያህል የሚገመት ነው። እርግጥ አካባቢውም ሆነ የቤቱ አቀማመጥ የደስ ደስ አለው። ግቢውን ሆነ ቤቱ ከማነሱ በስተቀር የጐደለው ነገር ላይኖር ይችላል። የኰንግሬሱ ምክር ቤት ሲሆን ዋሽንግተን ከተማ የሚሠሩት ህንፃዎች ሁሉ በስፋት እንጂ በቁመት ከምክር ቤቱ በልጠው እንዳይሠሩ በህግ የተከለከለ ነው ይባላል። በዚህም ምክንያት ተሰርተው የሚገኙት ፎቆች ሁሉ መጠነኛ ሆነው ይታየሉ። የዋሽንግተን ዲሲ ብዙ የኢትዮጵያን ምግብ ቤቶች ያሉ መሆናቸውን ተመልክተናል። ከጐበኘናቸውም ውስጥ (የእማማ ደስታ) የኢትዮጵያ ምግብ ቤት የሚባሉ ይገኙበታል።

የዋሽንግተን ዲሲ የሰነበትነው ላንድ ሳምንት ያህል በመሆኑ የሚያማምሩ የመናፈሻ ቦታዎችና የሃብታሞች መኖሪያ በሚባለው ቀበሌ የተሠሩት ህንፃዎች ግዙፍነትም ሆነ ውበት ያላቸው ናቸው። ከዚህ በተቀር የዋሽንግተንን እንደተመለከትነው መንፈስን የሚማርክና ጐልቶ የሚታይ ነገር አላገጠመንም።

## 7/ ቨርጂኒያ (VERGINIA)

በዋሽንግተን ዲሲ ከተማ ተያይዞ የሚገኘውን ቨርጂኒያ የተባለውን ስቴት ከተማውን (ኤልክሳንድርያን) ለመጐብኘት እድል አጋጥሞን ስለነበር በዚሁ ከተማ ባለው ሰማይ ጠቀስ ፎቅ አንድ ምሽት ተጋብዘን በነበረበት ወቅት በ18ኛው (ፎቅ) ላይ በነበረው የመጠጥና የመጫወቻ አዳራሽ ውስጥ ገብተን ስመለከት ቤቱና ዕቃዎቹ በጣም

ዘመናዊ ሆነው አዲስ የተሠሩ ሲሆኑ ለምሽቱ መዝናኛ ኦርኬስትራና ጥሩ ጥሩ ዘፋኞች ያሉበት ነው። የተቀመጠው ሰው ሁሉ በየግንባሩ የአሌክሳንድርያ ከተማን ለማየት የሚያመች በመሆኑ የከተማው መንገድና ኤርፖርቱ ጭምር በመብራት አሸብርቆ ይታያል። እኛም ከአደራሹ ባንዱ ክፍል ተቀምጠን እየተጋበዝን ከተማውንና ዘፈኑን ስንመለከት ባለንበት አቅጣጫ በኩል ክፍት የነበረው ስፍራ በቤቱ ግድግዳ በመዘጋቱ እንዲሁም ፊታችን የነበረው ኦርኬስትራና ዘፈን መንቀሳቀሱን ሳናይ ወደሌላ አቅጣጫ ተዛውሮ በመገኘቱ ሁኔታው አስገርሞን ሳለ ጋባዦቻችንም አስቀድመው ሳይገልፁልን "ከገባችሁ ጀምሮ ምን የተለወጠ ነገር ተመለከታችሁ?" ብለው ጠየቁን። እኛም "ይህ ግድግዳ ፊት ያልነበረ ሲሆን አሁን ከየት መጣ? ዘፋኞቹስ ከፊታችን ወደሌላ ክፍል እንዴት ዞሩ?" ብለን ጠየቅናቸው። እነሱም ይህ የተቀመጥንበት አዳራሽ ወለሉ ብቻ ምንም ሳይታወቅ የሚዞር መሆኑን ገለፁልን። በአዳራሹ ውስጥ የነበረው የሰው ብዛት መጠን የሌለው ስለነበረ እኛም የመሰለን ስመጥሩ የሆነችው ዘፋኝ በመኖር እሷን ለማየት መሰሎን ነበር እንጂ ሌላ ምክንያት ያለ አልመሰለንም። ግን የሰው የበለጠ ፍላጎትና ደስታ በሚሠራ አዳራሽ ውስጥ ተቀምጦ በመጋበዝና የአሌክስንድርያን ከተማን ለመመልከት መሆኑን ለመረዳት ቻልን።

በዚሁ ቀን ምሽት ያያነው ሌላው ደግሞ ድምፃዊ ተጫዋች የሆነቸውና በአዳራሹ ውስጥ በማስተናገድ ላይ በብዛት የሚገኙት ወጣት አሜሪካን ሴቶች በሙታንታ ልብስ ብቻ የሚታዩ ስለሆነ ነገሩ አስገርሞን ስናወጋ "እናንተ ከዚህ ትደነቃላችሁ ጨርሶ ሙታንታ ሳይኖራቸው የሚዘፍኑበት አዳራሽ አለ ወሬ ብቻ ሰምቶ ከመሔድ እናሳያችሁ" ብለው ከግብዣው በኋላ እተባለው ስፍራ ይዘውን ሔዱ። አዳራሹ ሰፊ ሆኖ ከጭለማው የተነሳ ብዙ ሰው ያለበት አይመስልም። ነገር ግን ያማረና የደመቀ ብርሃን ባለው እስቴጅ ላይ ፍፁም ራቁታቸውን ሆነው በየተራ የሚደንሱ ሴቶች ፈረንጆች አየን። እንዳገጣሚ ሆኖ የተቀመጥነው ወደ እስቴጁና ወደ ሙዚቃው ማሽን ቀረብ ባለው ስፍራ ስለነበረ በአርቲስት ስም የሚጠሩት ገላቸው ያላንዳች የጨርቅ ምልክት ተራቁቶ የሚታዩት ወጣት አሜሪካዊ

ሴቶች የሚያሳዩትን የዳንስ ትዕይንት በንግግር ቃላት ማሳረዳት አይቻልም። ሙዚቃው የሚመራው በማሽን ስለሆነ የምትፈልገውን ዘፈን የምታስታካክለው እራሷ ከእስቴጁ ላይ ወርዳ ነው። ስትደንስ ጨርሶ ድካም የሚባል ጠባይ የለባትም። የሰውነቷ አቋሟ በአጥንት የተያያዘ ስለማይመስል የምታደርገው እንቅስቃሴ ሁሉ ሰውነቷን እንደሚተጣጠፍ ጨርቅ በምትፈልገው ዓይነት ታጥፈዋለች፣ ትጠመዝዘዋለች። ይህም የአርቲስትነት ሙያ ለሚመለከተው ሁሉ ተደናቂነት እንደሚኖረው አያጠራጥርም።

የጉብኝት ጉዞአችንን በመቀጠል ከቨርጂኒያ በኋላ ስንጐበኝ ያቀድነው ኒው ጀርሲ የተባለውን ስቴት ነበር።

8/ ኒው ጀርሲ (NEW JERSEY)

በታሪክም ሆነ በለምነቱ እንዲሁም የኢ.ቃውንት መፍለቂያ የሆነው ኒው ጀርሲ የገባነው ሰኔ 30 ቀን 1972 ዓ.ም ነበር። እንደደረስንም በማዕግስቱ ኒው ጀርሲ ወሰን ላይ የሚገኘውን የፊላደልፊያና ሌሎችን ቀበሌዎች እየተዘዋወርን ለማየት ችለናል። ኒው ጀርሲ ከፋብሪካዎችም በቀር በእርሻ ለም የሆነ፣ በከተማ ውስጥ የተፈጥሮ ደንና ትካልቅ ወንዝም ያለበት ነው። መኖሪያ ቤቶችም ሆኑ የገበያ አዳራሾች ወይም ፋብሪካዎች ተራርቀው የተሠሩ ሲሆን አልፎ አልፎ በከተማው ወስጥ ሰፋፊ የእርሻ ሰብልም ይገኛል። የመንገዶቹም ብዛትና ስፋት የተለየ ውበት ያለው ሆኖ ይታያል። በፊላደልፊያ ከተማ ከጐበኘነው ልዩ ልዩ ስፍራዎች ሌላ ታሪካዊ ሆኖ የሚገኘው፣ የአሜሪካንን አገር የአስተዳደር አቋም ከዛሬ 200 ዘመን በፊት አሁን የሚታዳደሩበት ህገ መንግሥት የተረቀቀበት ተዘጋጅቶም የተፈረመበትን አዳራሽ በምንጐበኝበት ጊዜ በጣም ብዙ ቱሪስቶች የነበሩ ሲሆን እኛም ተራችንን በመጠበቅ ከነሱው ጋር ተሰልፈን በሙዚየም መልክ የተዘጋጀውን ታሪካዊ ስፍራ እየተዘዋወርን በጐበኘንበት ወቅት መጀመሪያ በዚያን ጊዜ የነበሩት አማካሪዎችና ትካልቅ ሰዎች የመከሩበት አዳራሽ፣ ከዚያም ሕግ መንግሥቱን ያረቀቁበትና የተከራከሩበት የተለየ አዳራሽ፣ በተስማሙም ጊዜ የተፈራረሙበት አዳራሽ፣ የአባሎቹ ወንበርና ብዙ ጠረጴዛዎች፣ ደብዘዝ ያለ አረንጌዴ መልክ ያለው ዘርፈፍ ያለ የጠረጴዛ ልብስ

እንዲከበስ ሲታይ፣ እያንዳንዱም አባል በየወንበራቸው ግንባር ባለው የቀለም ማዕድ ላይ በሥርዓት ተቀምጦ የሚታይ፣ የፈረሙበት የዶሮ ካባ ብዕር ጭምር ይገኛል። ረጅም ሰዓት በፈጀው ጉብኝት አስረጂዎቹ ሲገልጡልን ይህ በየክፍሉ የሚገኘው ዕቃና የተፈረመበትም የዶሮ ካባ ልክ የዛሬ 204 ዘመን ህገ መንግሥቱን ያዘጋጁት ሰዎች የተጠቀሙበት መሆኑን ደጋግመው ነግረውናል።

በአዳራሹ በኩል ያለው አዳባባይ በዘመኑ በተዘጋጀ ትልቅ ግንድ ላይ ተሰቅሎ የሚገኘውንም ታላቅ ደወል በምንጐበኝበት ጊዜ “ይህ ደወል አሜሪካንን ከዳር እስከ ዳር ድምፅ በማሰማት ስለ ህገ መንግሥቱ መመሥረት የምሥራች ቃል ያበሰረ መሆኑንም አስጐብኝዎቹ አጥጋቢ በሆነ መግለጫ በሚሰሙበት ጊዜ ከደስታቸው ስሜት የተነሣ ስለመስራቶቹ ጀግንነትና ችሎት እንደፉከራም በማድረግ ሲናገሩ እንባ ይታገላቸው ነበር። በዚህ ታሪካዊ በሆነ ሥፍራ ላይ ከዛሬ 200 ዓመት በፊት የነበሩትን ቤቶችና ደወሉን ጭምር፣ የአቀማመጡን ፕካን ባጭሩ ለመረዳት መጠነኛ የፅሁፍ መግለጫ ከዚህ ማስታወሻ ጋር ይገኛል። የኒው ጀርሲና የፊላደልፍያ ጉብኝት በዚሁ ተፈፅሞ ጉዞአችንን ወደ ኒዎርክ በመቀጠል የኒው ጀርሲ ወሰን ኒዎርክ ከተማ ውስጥ ድረስ ስለሆነ ወደኒዎርክ በምንጔዝበት ጊዜ የነበረው ያገር ውበት፣ የፋብሪካዎች ብዛት እንደፎቅና ምድር ቤት ሆኖ እንደ ጨርቅ በፈለጉት ዓይነት ተሸንሽኖ የሚታየው መንገድ መሀንዲሶቹ እንደት አድርገው እንደቀየሱት ከጐበኘናቸው የአሜሪካን አገሮች ከፍተኛውን ስምና ዝና ይዘው የሚገኙት የዚህ ዓይነቱ መንገዶች ናቸው

9/ ኒው ዮርክ (NEW YORK)

ኒው ዮርክ ከተማ ውስጥ እንደገባን በከተማው አጠገብ የሚገኘውን ባህር አቋርጦ ወደ ማህል ከተማ ለማለፍ መኪናም ሆነ ባቡር ከባህር በታች ባለው ጐዳና የሚጔዝ በመሆኑ እኛም በመጣንበት መስመር በኩል ከባህሩ በታች ወደ መሬት በመግባት ጉዞአችንን ቀጥለን ከኒዎርክ ማህል ከተማ ዳውንታውን ደረስን። የኒውዮርክን ከተማ ቀደም ሲል አሜሪካ አገር ስገባ ያየሁትና ለሁለት ቀናት ያህል የተመለከትኩትም ቢሆን በጉብኝት ፕሮግራም በስርዓት

ያካየሁት ስለነበረ ባሁኑ ወቅት በትራፊኩ ትርምስምስና መጨናነቅ ምክንያት በመኪና መዞሩ ትዕግስትን ስለሚያስጨርስ አብዛኛውን ጊዜ የምንዘዋወረው በምድር ውስጥ ባቡር ነበር። በመጀመሪያው ቀን ከጌደኛዬ ጋር የጐበኘነው የተባበሩት መንግሥታት ዋና መሥሪያ ቤትን ስለሆነ እንደሌሎቹ ሰማይ ጠቀስ ፎቅ ተወዳዳሪ የሆነው የዓለም መንግሥታት ሸንጐ ጽ/ቤት ከመሃል ከተማ ያልራቀ ቢሆንም አቀማመጡ ለየት ያለ ነው። ሰፊ አደባባይና ከኤርፖርትም ያካነሰ ሜዳ ፓርኪንግም አለው። እጅግ በሚያምረው አደባበዩ ላይ የዓለም መንግሥታት ባንዲራዎች በሥርዓትና ባማረ መልክ ሲውለበለቡበት በመታየት በጣም ያስደስታል። በተሰጠው ጠቅላላ ዓለም አቀፍ ምን ላይ እንደተገለጠው የ151 አባል መንግሥታት ሥም የሚገኝበት ሲሆን ሥም ዝርዝሩ ውስጥ ገባ ሲል በተባበሩት መንግሥታት አባልነት የተመዘገቡበትን ዘመን ያገራቸውን ስፋትና የህዝብ ብዛት ይገልፃል፡ ፡ በዚሁ ሊስት በአርባ አምስተኛው ተራ ቁጥር ተመዝግባ የምትገኘው አገራችን ኢትዮጵያም እንደ ኤውሮፓ ዘመን አቆጣጠር ከ1945 ዓ.ም ጀምሮ የተባበሩት መንግሥታት አባል መሆንዋን ሲያረጋግጥ ያገሪቱ ስፋት በኪሎ ሜትር ካሬ 1,221,000 እንደሚሆን የህዝቧም ብዛት እ.ኤ.አ. በ1978 ዓ.ም 29,705 ,600 መድረሱን ያረጋግጣል።

በመግቢያው ላይ የሚገኙትን የድርጅቱን ጥበቃ ክፍል ወታደሮች ፍቃድ ጠይቀን ወደ ውስጥ ከገባን በኋላ ወደ አሴምብሊው አዳራሽ ከመሔዳችን በፊት ከመግቢያው ወለል ገባ ብሎ በስተቀኝ ባለው ስፍራ በመታሰቢያ ስም ወርቅ በመሰለ መልክ ታሪካቸውና ስማቸው የተቀረፀውን ሠሌዳ ስንመለከት በተባበሩት መንግሥታት ድርጅት ከፍ ያለ አገልግሎት ካበረከቱት የተሰየመ ክፍል በመሆኑ እኛም እንደሌሎቹ ጐብኝዎች ጨለም ብሎ ወደሚገኘው ክፍል ገብተን የህሊና ፀሎት ለማድረግ ችለናል። በግድግዳው ሠሌዳ ላይ የሚታየው የወርቅ ፅሁፍ አንዱ ክፍል በኰርያ ጦር ሜዳም የወደቁትንም ወታደሮች ጭምር ስለሚገልፅ ቆራጥነትና ዝና ልባችን የኲራት መንፈስ ተሰማው።

በዚሁ አጠገብ ባለው ወለል ልይ በመስተዋት ውስጥ ሆኖ ለጐብኝዎች የሚታይ ከጨረቃ የመጣ ኰረት ድንጋይ ተመልክተናል። ቀጥሎ ወደ መሰብሰቢያው አዳራሽ አልፈን በመሰብሰቢያው አዳራሽ ልዩ ልዩ ክፍሎችን

ከተመለከትን በኋላ እዚያው በሪሴፕሽን አካባቢ በሚገኘው ውበቱ በሚማርከው ቡና ቤት ጐራ ብለን የምንፈልገውን በመጋበዝ በእንግዳ ማረፊያ አዳራሽ ጥቂት ዕረፍት በማድረግ ከቆየን በኋላ ተመለስን።

በሚቀጥለው ቀን የጐበኘነው ዳውንታውን በተባለው ማህል ከተማ የሚገኘውን ልዩ ልዩ የገበያ አዳራሽና ሱቆች ነበር። ነገር ግን የኒው ዮርክ ከተማ ሙቀት በጣም የሚያስጨንቅና የሚያስፈራ ስለሆነ እንዳሰብነው ኒውዮርክ ለአንድ ሣምንት ለመቆየት ባለመቻላችን ከጌደኛዬ ጋር ተሰነባብተን እሱ ወደ ለንደን ጉዞውን ሲቀጥል እኔም ስለጤና ጠቅላላ ምርመራ ጉዳይ ኒው ጀርሲ የሐኪም ቀጠሮ ስለነበረኝ ሁለተኛ ጊዜ አንድ ሣምንት ያህል ቆየሁ። በዚሁ ጊዜ ጠቅላላ የጤና ምርመራ ለማድረግ መልካም አጋጣሚ ስለገኘሁ ኒው ጀርሲ የልዩ ልዩ ፕሮፌሽናል ሐኪሞችና በከፍተኛ ሥም የታወቁ ሆስፒታሎች ያሉበት በመሆኑ በአንድ ሣምንት ውስጥ ምርመራው ተጠናቆልኝ ውጤቱም እጅግ ያስደሰተኝ ስለሆነ በዚያ በኩል ያለውን የህክምና ጉዳይ ጨርሼ እንደገና ከ3ኛ ጊዜ ወደ ነው ዮርክ ተመልሼ መጣሁ። ወደ ኒው ዮርክ የተመለስኩት በአውቶቡስ ስለ ነበር ይህ አገር አቋራጭ በጣም ፈጣን የሆነ የህዝብ ማመላለሻ አውቶቡስ ምቹቱ ከአውሮፕላን አያንስም ብዬ ብናገር ስህተት አይሆንም። መታጠቢያ ቤትና መዝናኛ ክፍልም አለው። ኒው ዮርክ እንደደረስኩ ሙቀቱን ለመቋቋም ስለአልቻልኩ ሁለት ቀን ብቻ ቆይቼ ከካሊፎርኒያ በመጣሁ በአንድ ወር ከአንድ ሣምንት ውስጥ ከኒው ዮርክ ሣን ፍራንሲስኮ ኤርፓርት ለመድረስ 5 1/2 ሰዓት በመብረር ጉዞዬን ከጨረስኩ በኋላ ልጆቼ ስለተቀበሉኝ የመጀመሪያው ዙር ጉዞ መግለጫ በዚሁ ያበቃል።

ለምሳሌ ያህል ከታዩትና ከሚነገሩት በተጨማሪ የተያዙ ማስታወሻዎች

ሀ/ በይበልጥ ብዙውን ጊዜ የአሳለፍኩት በሳን ፍራንሲስና አካባቢ በሣንታ ክላራ በተለይም ሣን ሆዜ ሲሆን በሌሎች በተዘዋወርኩዋቸው ለምሳሌ በትልልቆቹ ከተሞች እንደ ኒው ዮርክ፣ ችካጐ፣ ዋሽንግተን፣ ሎስ አንጀለስ፣ ኦሃዮ፣ ኢንዲያና፣ ኒው ጀርሲና ፊላደልፊያ ባሉት ሁሉ በአሜሪካን አገር የሚገኙት ሸቀጦች ወይም በጠቅላላ የኢንዱስትሪና የፋብሪካ ውጤቶች ያሉባቸው ምንም ያህል ልዩ ልዩ ቅርፅ ይኑራቸው እንጂ ዓይነታቸው ምንም ያህል ልዩነት የለውም። ከላይ ስማቸው

ከተጠቀሰው ትላልቅ ከተሞች ሌላ አነስተኛ በሆነው በሳን ሆዜ ከተማ ያለውን የአንድ አካባቢ ሱቅ ለምሳሌ ያህል ልግለፅ። ቤቱ በተጣለለ ሜዳና ፓርኪንግም በየአቅጣጫው በሚገባ በተዘጋጀ ስፍራ ላይ በፎቅ መልክ የተሠራ ነው። ወደሱቁ መግቢያ በር ዙሪያውን አለው። በቤቱ መካከል ከላይ ክፍት ሆኖ ፏፏቴና ወራጅ ውሃ በቦታው ይታያል። በዚሁ አካባቢ የህዝብ መዝናኛና መቀመጫዎች በብዛት ይገኛሉ። የሱቁ ሥም ኦልድ ሚል ሾፒንግ ሴንተር OLD MILL SHOPPING CENTER ይባላል። በውስጡ ለሰው ኑሮ የሚያስፈልገው  ሁሉ ተሟልቶ ይገኛል። በዚሁ ሱቅ ወይም የገበያ አዳራሽ ለአገር ውስጥም ሆነ ለኢንተርናሽናል ወሬ ማሰበራጫ አንድ ሬድዮ ጣቢያ ስቱዲዮ፣ ስድስት የሲኒማ ቤት አዳራሽ እነዚህ በፊልም ዓይነት ውድድር የሚያደርጉት ናቸው። ልዩ ልዩ ከፍተኛና አነስተኛ ሆቴልና ምግብ ቤቶች አሉ። ከነዚሁ አንዳንዶቹ የቻይና፣ የጀርመን፣ የኢጣሊያ፣ የፈረንሣይ፣ የግሪክ፣ የራሺያና የአሜርካን ሲሆን በመዝናኛው ክፍል ባለው የኦርኬስትራ አዳራሽ ድማፃዊ ተጫዋቾች ተመልካችን ያስደስታሉ፡፡ እንዲሁም እንደ ኰክቴል በሆኑ ክፍሎች ደግሞ የሚፈለገው ዓይነት መጠጥም ሆነ ሌላ ከፎቁ ላይ ወደ ውስጥ ከማየት በተዘጋጀው መቀመጫ ላይ ሆነ እየተጋበዙ ፏፏቴና ዓሣዎች የሚጨፍሩበት ባህር ይታያል። በሌላ በኩልም ቤተ መጻሕፍትና እንደ ሙዚየም በሆነ አዳራሾች ልዩ ልዩ ጥንታዊ የሆኑ የየሀገሩ ዕቃዎች ደምቀው ይታያሉ። የባንክ አገልግሎቶችም በየክፍሉ ይገኛሉ። እንግዲህ ይህ አንድ ሱቅ ተብሎ ይጠራል እንጂ የራዲዮ ጣቢያ ወይም ሲኒማና ሆቴል ተብሎ አይጠራም። ሱቁ ላይ እንደገለፀው ለሰው የሚያስፈልገው ሁሉ የሚገኝበት ውስጥ ለውስጥ ሲሄዱ ታይቶ የማያልቅ ነው። ስለዚህ ሱቆች ሲባሉ ብዙዎቹ በአዳራሽ መልክ ዓይነት የተዘጋጁ ናቸው።

ለ/ አሜሪካኖች በሣይንስና በቴክኖሎጂ ከሌላው ዓለም ቀድመው የሚገኙ መሆናቸውን ሥራቸው ይመሰክራል። በአሁኑ ጊዜ ወደፊት ለ20 ዓመታት የሚያስፈልገውን ጥናት አጠናቀውና አምነውበት ሥራውን ለሚያንቀሳቀሰው ለኰምፒውተሩ አዘጋጅታው የሚገኙ መሆናቸው ይነገራል። እንግዲህ ወደፊት 20 ዓመታት የሚፈጀውን ሥራ ዛሬ ጨርሰው ከተገኙ ሌላው ዓለም እነሱ ዘንድ ለመድረስ የሚፈጅበትን ጊዜ ማሰብ ነው። ከ20 ዓመታት በኋላ ደግሞ እርምጃው የዚህኑ ያህል እርቆ ስለሚገኝ እዚህ ላይ መመልከት የሚገባው በዚህ ዓይነት ፍጥነቱ ምን ጊዜም

የሚያቋርጥ መሆኑን ነው። ዛሬ ማናቸውም ሥራ ሲንቀሣቀስ የሚታየው በኰምፒውተር ሲሆን አብዛኛው የትምህርት አሰጣጥና ፍላጐት ወደ ኰምፒውተር ባለሞያነት እየተለወጠ ይታያል።

ሐ/ በአሜሪካን አገር ሶሳይቲ በኩል ሲታይ አገሩ እጅግ በጣም ሰፊ እንደመሆኑ መጠን ባህላቸው በየቦታው የተለያየ መልክ ቢኖረውም አብዛኛው ክፍል የሚጠቀምበት አንዳንድ ጐልቶ የሚታይ ነገር አለ።

ለምሳሌ አንድ ሰው ብዙ ወይም አንድ ልጅ ቢኖረው እስከ 12ኛ ክፍል ድረስ አስተምሮ ሴት ስትሆን እስከ 18 ወንድ ደግሞ ቢበዛ እስከ 21 ዓመት ድረስ ከወላጆች ጋር ቆይቶ ከዚያ በኋላ ራስን ችሎ መኖር ግዴታ ነው። ቢፈልጉ እየሠሩ ይማራሉ፤ ካልፈለጉም ሚስት አግብተው ወይም ጓደኛ ይዘው ይኖራሉ። እናት አባታቸውም ቤት ሆነው ከትምህርት ጋር ሥራ እየሠሩ ከሚያገኙት ደምወዝ ለኑሮአቸው የሚያስፈልገውን ወጪ የተወሰነ ገንዘብ ለቤተሰቦቻቸው መክፈል አለባቸው።

አባት እናት በእርጅና ምክንያት ሲደክሙ ሀብታሞች ከሆኑ ገንዘባቸውን ይዘው ወደሚስማማቸው አገር ሔደው ይቀመጣሉ። ድሆችም ከሆኑ ልጆቻቸው የመጦር ግዴታ ስለሌለባቸው የጡረታ ቤት ተብሎ በየቦታው የተቋቋመ ድርጅት ስላለ ልጆቹ እዚያው ወስደው ያስቀምጡዋቸዋል። የሚከፍሉት ነገር የለም። አንዳንድ ሃብታሞች ገንዘባቸው በጐ አድራጐት ድርጅት ስለሚሰጡ ብዙ ጊዜ ከልጆቻቸው ውርስ አያስተላልፉም። እድሜያቸው ከ65 ዓመት በላይ የሆኑት ወንዶችም ሆነ ሴቶች በአውቶቡስ በሚዘዋወሩበት ጊዜ አይከፍሉም፣ ነፃ ነው። ሆቴል ቤትና ምግብ ቤት ገብተው ምግብም ሆነ መጠጥ ከተጋበዙ በኋላ የሚከፍሉት ግማሽ ዋጋ ሲሆን ለዚሁ አገልግሎት ተብሎ ከአገሪቱ ተወላጆች ፎቶግራፍ ያለበት የተለየ ካርድ አላቸው። የውጪ አገር ሰዎች ደግሞ በፓስፖርታቸው ይጠቀማሉ።

ባንድ ፊት ደግሞ የአሜሪካ ሶሳይቲ አንዳንድ ቦታ እንደሚነገረው ምቾት ሰልችቷቸው ቤት ንብረታቸውን በመተው የኤሌትሪክ አገልግሎት፣ የስልክና የትራንስፖርት አገልግሎት ባለመፈለግ ምግብም እንደፈለጉት በማይገኝበት ቦታ ሆነው በደንበኛ ልብስና ጫማ ካለመጠቀም፣ ተቆጥበው ለመኖር የወሰኑም ይኖራሉ ይባላል።

እንዲሁም በሌላ በኩል አንዳንዶቹ እንደ ቀም ነገር በመቁጠር እጨረቃ ላይ ቦታ ከመመራት የምትፈልጉ እየተመዘገባችሁ የቦታውን ካርታ በአንዳንድ ብር ልትገዙ ትችላላችሁ እያሉ በደንብ የተዘጋጀ የቦታ አቀማመጥ ካርታ እየመዘገቡ ሲሸጡ ካርታውን የሚገዙበትም ዋጋ እንዳለው በመገመት ያምኑበታል እየተባለ ይነገራል።

በሌላ አንፃር ደግሞ ወደ ጨረቃ የተደረገውን የጠፈር ጉዞ በመቃወምና ፈፅሞ ባለማመን ጠፈረተኞቹ ጨረቃ ላይ ያልደረሱና ሊደርስ የማይችሉ መሆናቸውን የሚያወግዙ ክፍሎች መኖራቸው የሚያወሩ ክፍሎች ከዚህም ሌላ በማህበራዊ ኑሮ በኩል ጥቂቶቹ ሰብዓዊ ርህራሄ የጐደለው ጭካኔ ይታይባቸዋል። አንድ ሰው ቤተሰቦቹን በሙሉ (ሚስትም ሆነ ልጆቹን) ወይም ሌላ የውጪ ሰዎች በተለይም ወጣትነት ያላቸውን ልጆች የሚያስቅቅ ሁኔታ ይገድሉና መግደላቸውንም ወይም አምነው ሲያሳውቁ ከመግደልህ ምን ማስረጃ አለህ በማለት ወንጀለኛው የፈፀመው ድርጊት እንደ ቀላል ነገር ይቆጠራል ይላሉ። ይህ መቼም ከሚሰሙትና ከሚነገሩት ሁኔታች አንዳንዱን ለመጥቀስ ያህል ነው።

ከዚህም በቀር ደግሞ በጣም የሚያስገርመው ለሰሚም የሚቀፈው የቅሬታ ስሜት የሚያሣድረው እግዚአብሔር በጥበቡ የፈጠረውን የሰው አካል (የፆታ አቋም) በቀዶ ጥገና ወንዱን ወደ ሴትነት ሴቷን ወደ ወንድነት ለመለወጥ የሚሞክሩና የሚጥሩ ያደረጉም አሉ ይባላል። እንዲሁም ወንድና ሴት ባልና ሚስት ወይም ጓደኛሞች መሆን ሲገባቸው ወንድ ለወንድ፣ ሴት ለሴት በጓደኝነት እንደባልና ሚስት ሆነው ይኖራሉ። ይህም እራሱ እግዚአብሔር ያዘዘውን እንደመሻር የሚቆጠር ስለሆነ ሰብዓዊ ፍጡር የሆነ ሁሉ ሊያወግዘው የሚገባ ይመስላል።

ከዚህ በላይ የተነገሩት በአንዳንድ ጥቂት ሰዎች የሚፈፀሙ መሆናቸውን ለማወቅ ያህል የተገለፀ እንጂ እጅግ በሰለጠኑት በዚሁ በአሜሪካን አገር በአብዛኛው ክፍሎች በሚገኙት አብያተ ክርስቲያናትና በሚሲዮናውያን በሚተዳደሩ ዩኒቨርስቲና ኰሌጆች ሁሉ የእግዚአብሔር ታላቅነት የማይወደስበትና የማይቀደስበት የለም። ከብዙዎቹ አንዱ በኦክላሆማ ስቴት ውስጥ የሚገኝ ያንድ ትልቅ ዩኒቨርሲቲ ፕሬዘዳንት ፕሮፌሰር በየሣምንቱ ዕሁድ ረጅም ጊዜ በሚፈጅ የእግዚአብሔር ምሥጋና ክርስቶስ ለሰው ልጆች ደህንነት መድኃኒት ስለመሆኑ በሚያሰማበት ጊዜ

የእግዚአብሔርን ታላቅነት ሲገልፅ የሃያላን ሁሉ በላይ ከታላቅነቱም ፍፁም ወደር የሌለው መሆኑን እጅግ በሚያስደንቅ ከልብ በመነጨ ስሜት ደስታውንና ምስጋናውን ሲናገር እንባ እየተናነቀው ንግግሩን ያቋርጠው ነበር። በቴሌቪዥን አማካይነት የሚያስማውንም መንፈሣዊ ንግግር ሁሉም ያዳምጠዋል። በቅርቡ ለአሜሪካን ህዝብና ለሌላውም ዓለም በቴሌቪዥን ይታይ የነበረው ኒው ዮርክ ውስጥ የአሜርካን ፕሬዚዳንትና ም/ፕሬዚዳንት የካቢኔና የኰንግሬሱ አባሎች እንዲሁም የስቴቱ የተሰበሰቡት ሁሉ የተገኙበት 8 ቀን የፈጀ ታላቅ ስብሰባ በጉባዔው መደምደሚያ ላይ እጅግ በጣም ብዙ ህዝብ በተሰበሰበበት ወቅት ሰብሰባቸውን በፀሎት የዘጉት አንድ የሃይማኖት ምሑር የሆኑ እግዚአብሔር ታላቅ ሃያል የገዥዎች ገዥ በመሆኑ በመላው ዓለም ሠላም ያውርድ፣ ከሰላም የሚበልጥ የለም፣ በሰብሰባችንም የተደረገውን ውይይት ይባርከው ሲሉ በሃይማኖት በኩል ያላቸውን ጠንካራ እምነት ሲገልጡ አዳማጩም በተመስጦና በልባዊ ስሜት ይመለከት ነበር። እንግዲህ እግዚአብሔር የሁሉም በላይና ሃያል ገናና መሆኑን በመቶ ዘጠና ዘጠኙ ያመኑበት ሲሆን ጥቂት በሆኑ ወገኖች ላይ የሚታየው ተፈላጊ ያልሆነ አስከፊ ሥርዓት በሰው ላይ ጥፋት ወይም መቅሰፍት ከማስከተል በቀር ዋጋና ጥቅም ሊኖረው አይችልም። ማናቸውም ጉዳይ ደግሞ ሆነ ክፉ ሊፈፀም የሚችለው በእግዚአብሔር ፈቃድ እንጂ በሰው ጥበብና ሃይል አለመሆኑን መገንዘብ ከአዋቂነትም አስተዋይነት ነው።

በገንዘብ፣ በጥበብም ሆነ በሌላ ኃይል ሊፈፀም የማይቻለው እግዚአብሔር ሲፈቅድ ከመቅፅበት ይፈፀማል። በሱ ፈቃድ ካልሆነም አይፈፀምም። ትንሽ ትልቅ ሳይል ለሁሉም ቸርነቱንና ምህረቱን ለሚሰጥ ፈጣሪ ድካም የሌለበትን መሥጋና ከማቅረብ ለሚቦዝኑ ምንጊዜም ትዕግስቱ ወሰን የሌለው መሆኑንም ማመን አስተዋይነት ነው።

መ/ በአሁኑ ጊዜ በአሜሪካን አገር በተለይ በካሊፎርኒያ የሚገኙት ኢትዮጵያውያን ተማሪዎች አብዛኞቹ እየሠሩ የሚማሩ ናቸው። አልፎ አልፎ በአንዳንድ ሚሲዮኖች አማካይነት ካልሆነ በስተቀር የግል እስኰላርሺፕ ወይም ነፃ ትምህርት ለማግኘት ያዳግታል። እየሠሩ ከሚማሩት ልጆች በይበልጥ ሴቶቹ ለሥራ በገንዘብ ቁጠባ በኩል ብልጫ አላቸው። ለምሳሌ ቀንና ሌሊት ሳይመርጡና ዕረፍትም ሳይፈልጉ

ሁለትና ሶስት ሥራ በመስራት ገንዘብ አጠራቅመው ደህና ቤት ተከራይተው የቤት ዕቃዎችንም አሟልተው መኪናም ከገዙ በኋላ ሥራውን በመቀነስ ያላቸውን ጊዜ ወደ ትምህርት ፕሮግራም አመዝነው ትምህርታቸውን ይከታተላሉ። ይህም ከነባሮቹ እንጂ አዲስ ከሚመጡት አይደለም። ለአዲስ ተማሪዎች የአሜሪካን አገር ኑሮ ቀላል አለመሆኑን ማወቅ ያስፈልጋል። አሜሪካን አገር በመምጣት ብቻ ለመማርም ሆነ ለመኖር በጣም አስቸጋሪ ነው። እህት፣ ወንድም ወይም መጠጊያና ጌደኛ ያላቸውም ቢሆኑ ቢያንስ 12ኛ ክፍል አገራቸው የጨረሱ መሆን አለባቸው። ምክንያቱም በመጠኑም ቢሆን ሥራ ይዞ ለመማር ይረዳዋል። ችግሩንም መከላከል ይችላሉ።

ይህን ዕድል ሳያገኙ ካገራቸው የወጡት ልጆች ያለባቸው የኑሮ ችግር በቀላሉ የሚገመት አይደለም። ማናቸውም የጉልበት ሥራ ቢገኝ እንኳን ለትምህርት ጊዜ አመቺ ስላልሆነ ካለመማራቸውም ሌላ በኑሮ በኩል ያላሰቡት ችግር ያጋጥማቸዋል። አቋማቸው እራሳቸውን ለመርዳት ሆኖ ሲገኝ ከሚረዷቸው ጋር ተደጋግፎ ለመኖር ያበቃቸዋል። ስለዚህ ትምህርታቸውን ለማስፋፋት ዕድል አጋጥሟቸው የሚሄዱት ሁሉ እዚያ ከደረሱ በኋላ ሁኔታው እንዳያሳዝናቸው አስቀድሞ ከሚቀበሏቸው ወይም ትምህርት ቤት ከፈለጉላቸው የሚሰጣቸውን ምክር በጥሞና ማሰብና መፈፀም ስለሚጠቅማቸው ይህንኑ ቢያውቁት መልካም ነው።

አሁን እዚያ የሚገኙት የኔ ልጆች ሁለት ወንዶችና አንዲት ሴት ሲሆኑ ትልቁ ልጅ ወንዱ ቀደም ብሎ በራሱ ጥረት ተጻጽፎ ባገኘው እስኰላርሺፕ (ነፃ ትምህርት) ከቤተሰቡ ወይም ከመንግሥት አንዳች ወጪ ሣይጠይቅ በ1963 ዓ.ም ሔዶ የመጀመሪያውን በማቴማቲክስና በቴሌኰምዩኒኬሽን የባችለር ዲግሪውን (BACHLOR OF SCIENCE IN MATHEMATICS AND TELECOMMUNICATIONS) ከአገኘ በኋላ ትምህርቱን በመቀጠል በሒሳብ ኤጁኬሽን የማስትሬት ዲግሪውን ተቀብሏል።

እንዲሁም ትምህርቱን በማስፋፋት ለሶስተኛ ጊዜ በኢንጂነሪንግ ባለሙያነት ኢንጂነር በመሆን (ENGINEERING) የማስትሬት

ዲግሪ ተቀብሎ አሁንም ትምህርቱን ወደ ከፍተኛ ደረጃ በማሳደግ ላይ ስለሚገኝ ከጥቂት ጊዜ በኋላ ዶክትሬቱን ያገኛል።

ሌሎቹ ሁለቱ፣ ወንዱ በኰምፒውተር ጥናት ሴቷ ደግሞ በዚሁ በኰምፒውተር ሙያ ለመመረቅ ትምህርታቸውን እያኪያሔዱ ናቸው።

ሠ/ በመጨረሻ ጊዜ የታሆ ሃይቅና የኔቫዳ ስቴት ጉብኝት

ኔቫዳ የተባለው ስቴት ከምሥራቅ ካሊፎርኒያ ጋር የሚዋሰን ሲሆን የሚገኘው ታሆ ከሚባል ከታወቀ የህዝብ መናፈሻና መዝናኛ ከተማ ሃይቅ ወሰን ባህሩን ለሁለት ስቴቶች ከፍሎ የባህር አቀማመጥ እንዲሚታየው አንዱን ክፍል የካሊፎርኒያ ግዛት ለሆነው ለታሆ ከተማ አንዱን ክፍል ደግሞ ለኔቫዳ ስቴት ወደ ሬኖ ከተማ ወገን አድርጐ በማካፈል በባህሩ ሥዕል ላይ እንደ መስመር ሆኖ ይታያል። ከሣን ሆዜ ወይም ከሣንፍራንሲስኮ ያለው ርቀት 200 ማይል ነው። እነዚህ ሁለቱ አገሮች ካሊፎሪኒያና ኔቫዳ ተካፍለውት የሚታየው ባህር አቀማመጡ ዙሪያውን በጣም ከፍተኛ የሆነ በረዶ የሚከማችበት ጋራ የከበበው የጋራው ሥር ዙሪያውን ረባዳና ከተማውም በሙሉ አያሌ ዘመናት ዕድሜ ባለው ለኢንዱስትሪ አገልግሎት በሚውሉ ደኖች የተሸፈነ ነው።

ሃይቁ ዙሪያውን በጣም ምቹ የሆነ አስፋልት መንገድ አለው። የሃይቁ ውሃ ከማንኛውም ባህር በተለየ መልክ የሚታይበት ደግሞ በውሃውና ከውስጡ ጥራትና ፅዳት የተነሳ በባህሩ ላይ በሚንሸራሸሩት ጀልባዎች ላይ ሆኖ በባህሩ ውስጥ ርቀትም ሆነ በቅርብ ጥልቀት የሚገኙትን ማንኛውም ነገሮች ሁሉ ቁልጭ አድርጐ ማሳየቱ ነው።

የታሆ ከተማ ምንም ውፍረታቸውና ብዛታቸው ጐልቶ በሚታየው የደን ዛፎች የተጣበበ ቢሆንም ከባህሩ ሁለት ኪሎ ሜትር ራቅ ብሎ የአውሮፕላኑ ማረፊያ ሲሆን የባህሩን ዳርቻ ይዞ መደዳውን ሆቴሎችና የጀልባዎች መሳፈሪያ ጣቢያ በብዛት የሚገኙበት ነው፡ ፡ በከተማው ውስጥ ያሉት ቤቶች ሦስት አራተኛው እጅ ለሆቴል አገልግሎት የተሠሩ ናቸው። በዚሁ የሁለት አገር ይዞታ ሃይቅ ዳርቻ

ወደ ኔቫዳ ክፍል በሆነው ከሁለት ቦታ ላይ በከፍተኛ ሥምና ዝና የታወቁ ሃራስና ሣሃራ የተባሉ የቁማር መጫወቻዎች ከሙሉ የሆቴልና የልዩ ልዩ የሸቀጣ ሸቀጥ ሱቅ በተሟላ ሁኔታ ተዘጋጅተው ይገኛሉ። ከምሣሌ ያህል እንደተረዳነው ያንዱ ክፍል የቁማር መጫወቻ ድርጅት መደበኛ ሠራተኞቹ 6000 (ስድስት ሺህ) ሲሆን በመኪና ማቆሚያው ፓርኪንግ ከሠራተኞቹ ብቻ በተመደበው ከአምስት ሺህ ያካነሠ ለእንግዶች ደግሞ ከአስራ አምስት ሺህ በላይ የሚገመት መኪና ይታያል። የፓርኪንጉን ሜዳ ከሆቴሉ ፎቅ ላይ ወጥቶ እንጂ ከመሬት ላይ ሆኖ አቀማመጡንና ብዛቱን ለመገመት ያዳግታል። በአስራ ስምንተኛው ፎቅ ላይ ትልቅ የምግብ ቤት አዳራሽ ስላለ እኛም ለመመልከት የቻልነው በዚሁ ስፍራ ሆነን ነበር። ይህ የምግብ ቤት አዳራሽ በባህላዊ አሠራር ያማረ በአርት ሥራዎች ብረትን እንደ እርጥብ ቅጠልና አበባ፣ እንደ ለምለም ሣርና ቁጥቋጦ በማድረግ የአርቱ ባለሞያ የተራቀቀበት ሆኖ ይታያል። ከዚህ በላይ ስለመኪናዎች ብዛት እንደተነገረው በአውሮፕላን በባቡርና በአውቶቡስ የሚጓዘው ሲጨመር የህዝብ ብዛት የቱን ያህል እንደሚሆን ለመገመት አያዳግትም።

ይኸው የቁማር ድርጅት በየዓመቱ ለአንድ ሣምንት ለሆቴል የሚያስፈልገውንና የትራንስፖርቱን ደርሶ መልስ ችሎ አሥር ሺህ ትካልቅ ሃብታሞችን በነፃ እየጋበዘ ያስተናግዳል። ይህ የተጠቀሰው ለአንዱ ክፍል ድርጅት ስለሆነ በዚሁ በኔቫዳ ስቴት በታሆ ሃይቅና ቦሬኖ ከተማ የሚገኘው የቁማር ድርጅት ብዙ ስለሆነ በየአንዳንዱ ክፍል ያለውን መጠን በዚሁ መገመት ይቻላል። የሚሠራው ሃያ አራት ሰዓት ያለማቋረጥ ስለሆነ የሰው ቁጥር ምንጊዜም የማነስና የመብዛት ልዩነት አያሳይም። እርግጥ መደዳውን የህዝብ በዓል በሆነ ጊዜ የሆቴል ማረፊያ በፍፁም ባለመኖሩ በየድንኳኑ ሰፍሮ ከሚታየውም በላይ ህዝቡ በየመኪናው ይገኛል። በዚህ ዓይነት ህዝቡ እንደ ሱስ ሆኖበት ለቁማር ጨዋታ ሲል ሃያ አራት ሰዓት ሲጉርፍ የሚያሣየው ሠርቶ የሚያገኘውን ገንዘብ የሚያስረክበው ለቁማር ነው ማለት ይቻላል። ምናልባት በመቶ አሥር የሚሆነው መጠነኛ ዕድል የሚያጋጥመው ይሆናል። የቀረው ግን ገንዘቡን እያረገፈ የሚሄድ በመሆኑ በጣም ያስገርማል።

በአሜሪካን ውስጥ ካሉት አገሮች የዚህ ዓይነቱ የቁማር ጨዋታ ቀደም ብሎ የተፈቀደው ለኔቫዳ ስቴት ብቻ በመሆኑ በዚሁ ስሙ በተጠቀሰው በሃይቁ አካባቢ ባለው ከተማ ከቁማርና ከሆቴል ድርጅት በስተቀር ሬኖ ላይ ብቻ

አንድ ኰሌጅ ሲኖር ሌላ ፋብሪካና ከፍተኛ ትምህርት ቤት የለም። ህዝቡ በሞላ የሚተዳደረው በነዚሁ ድርጅቶች ሆኖ አብዛኛው ቁማር ተጫዋቾች ከሌላ ስቴት በብዛትም ከካሊፎርኒያ የሚመጡ መሆናቸው ይነገራል።

የታሆን አካባቢ ሃይቅ ለመጐብኘት የሄድነው በአውቶሞቢል ስለሆነ ከሣንፍራንሲስኰ ጀምሮ እስከ ኔቫዳ ወሰን ድረስ ያለው አብዛኛውን የእርሻ አገር ሆኖ በብዛት ደን ያለበት ገደልና ጋራ ሆኖ በየቦታው አልፎ አልፎ ለህዝብ መዝናኛ የሚሆኑ ድርጅቶች ይገኙበታል። ቦታውም ሃይቅ ዳርቻ ላይ ከሚገኙት ሆቴሎች ማረፊያ ለማግኘት እድል አጋጥሞን ስለነበረ ያረፍንበት ቤት ልክ ባህሩን ተጠግቶ የተሠራ በመሆኑ ከቦታው ውበት ጋራ በምቾት በኩል የነበረው ዝግጅት ምንም የሚጐድለው አልነበረም።

ረ/ በካሊፎርኒያ - ሳንሆዜ በቆየሁበት ጊዜ የነበረኝ የጊዜ ማሳለፊያ ፕሮግራም ቀጥሎ እንዳለው ነበር፦

ጠዋት ከ12 ሰዓት እስከ 1 ሰዓት ተኩል ፀሎት

ጠዋት ከ1 ሰዓት ተኩል እስከ 2 ሰዓት ተኩል ሩጫ

ጠዋት ከ3 ሰዓት እስከ 3 ሰዓት ተኩል ዋና

ጠዋት ከ3 ሰዓት ተኩል እስከ አራት ሰዓት ተኩል ቁርስ

ጠዋት ከ4 ሰዓት ተኩል እስከ 7 ሰዓት ተኩል የጥናትና ማንበቢያ ጊዜ

ጠዋት ከሰዓት በኋላ ከ7ሰዓት ተኩል እስከ 8 ሰዓት ተኩል ምሣ

ጠዋት ከሰዓት በኋላ ከ8 ሰዓት ተኩል እስከ 10 ሰዓት ተኩል የዕረፍት ጊዜ

ጠዋት ከሰዓት በኋላ ከ11 ሰዓን እስከ 12 ሰዓት ተኩል የእግር መንገድ የተለመደ ፀሎት ስለሆነ ግማሽ ሰዓት የመልበሻና የፅዳት ጊዜ ነው። ሩጫው ከአንድ ሰዓት የተመደበ ስለሆነ 3 ½ ሰዓት ወደ ዋናው ሰፈር ይገባል። ከአሥራ አምስት ደቂቃ በሙቅ ውሃ ውስጥ ገብቶ ሳይንቀሳቀሱ መቀመጥ ከዚያ ወደ መዋኛው በመዘዋወር 45 ደቂቃ የዋና እንቅስቃሴ ቀጥሎ አሥር ደቂቃ ሻወር ከተደረገ በኋላ ወደቤት ተመልሶ ቁርስ በመጋበዝ እቤት

መቆየትና መፅሐፍ ማንበብ። እስከ 8 ½ ሰዓት ምሣ ሆኖ ከምሣ በኋላ የቀን ዕረፍት መኝታ። በአሥር ሰዓት ተኩል ለሻይ ግማሽ ሰዓት ቆይቶ እስከ አሥራ ሁለት ተኩል ባለው ጊዜ ወደ መናፈሻ ሥፍራዎች ወይም በፈለጉት መስመር የእግር መንገድ እንቅስቃሴ። ከ12 ½ ሰዓት በኋላ የጥሪ ግብዣ ከሌለ በጤና ምክንያት ወይም ከአዲስ አበባ የመጡ እንግዶች እንዳሉ እነሱን መጠየቅ፤ ከሌለም ወደቤት ገብቶ እስከ ምሽት 4 ½ ሰዓት ድረስ ቴሌቪዥን መመልከትና ዜናዎችን ማዳመጥ ነው።

# የፎቶግራፍ ትዝታዎች

1. የቡልጋ ማስታወሻ
2. የተቀደሰ ጋብቻ

   አጥላው ወልደ ዮሐንስ እና ሐመረ ገብረፃድቅ

3. የፍሥሐ ትዝታዎች
4. የናትናዔል ፍሥሐ አጥላው ትዝታዎች

   NATNAEL FESSEHA ATLAW'S MEMORIES

5. የልጅ ልጆች
6. ልጆች
7. ወዳጅ ቤተሰብ
8. ልዩ ልዩ ማስታወዋሻዎችና ደብዳቤዎች
9. የአሜሪካ ጉብኝት

የዳዊት መዝሙር 23።

እግዚአብሔር እረኛዬ ነው፥ የሚያሳጣኝም የለም።
በለመለመ መስክ ያሳድረኛል፤ በዕረፍት ውኃ ዘንድ ይመራኛል።
ነፍሴን መለሳት፥ ስለ ስሙም በጽድቅ መንገድ መራኝ።
በሞት ጥላ መካከል እንኳ ብሄድ
አንተ ከእኔ ጋር ነህና ክፉን አልፈራም፤
በትርህና ምርኵዝህ እነርሱ ያጽናኑኛል።

በፊቴ ገበታን አዘጋጀህልኝ በጠላቶቼ ፊት ለፊት ራሴን በዘይት
ቀባህ፥ ጽዋዬም የተረፈ ነው።
ቸርነትህና ምሕረትህ በሕይወቴ ዘመን ሁሉ ይከተሉኛል፥
በእግዚአብሔርም ቤት ለዘላለም እኖራለሁ።



አጥላው ወልደ ዮሐንስ



አጥላው ወልደ ዮሐንስ

1912 - 1995

ምስጉን ነው በክፉዎች ምክር ያልሄደ፥ በኃጢአተኞችም መንገድ ያልቆመ፥

በዋዘኞችም ወንበር ያልተቀመጠ።

ነገር ግን በእግዚአብሔር ሕግ ደስ ይለዋል፥ ሕጉንም በቀንና በሌሊት ያስባል።

እርሱም በውኃ ፈሳሾች ዳር እንደ ተተከለች፥ ፍሬዋን በየጊዜዋ እንደምትሰጥ፥

ቅጠልዋም እንደማይረግፍ ዛፍ ይሆናል፤ የሚሠራውም ሁሉ ይከናወንለታል።

ክፉዎች እንዲህ አይደሉም፥ ነገር ግን ነፋስ ጠርጎ እንደሚወስደው ትቢያ ናቸው።

ስለዚህ ክፉዎች በፍርድ፥ ኃጢአተኞችም በጻድቃን ማኅበር አይቆሙም።

እግዚአብሔር የጻድቃንን መንገድ ያውቃልና፥ የክፉዎች መንገድ ግን ትጠፋለች።

መዝሙረ ዳዊት 1

ዲማ ማተሚያ ቤት አዲስ አበባ 2012